# እፎይታ

፫ኛ ዓመት ቁጥር ፫ ህዳር ፲፱፻፺፩

ቆይታ ከጂቡቲው ፕሬዚዳንት ጋር



## በዋጋዱጉ የተቀጣጠለው ስብሰባ ፈንጂ...




# ዝቋላ ስቲል ሮሊንግ ሚል
# ZQUALA STEEL ROLLING MILL



በአመራረት ሂደቱና
በማምረት አቅሙ
የመጀመሪያ የሆነው ዝቋላ
ስቲል ሮሊንግ ሚል
**Prime Steel Billet**
በጥሬ ዕቃነት በመጠቀም



1. የአርማታ ብረቶች ከ 10 ሚ.ሜ ___ 32 ሚ.ሜ
2. ጠፍጣፋ ብረቶች ከ20 x 5 -12____ 50 x 5 - 12
3. ድፍን አራት ማዕዘን ብረቶች ከ10 x ሚ.ሜ ___ 20 x 20 ሚ.ሜ

**እያመረተ ለተጠቃሚዎች በማቅረብ ላይ ይገኛል።**



**ዝቋላ ስቲል ሮሊንግ ሚል**



↓

**መጥተው ይጎብኙን**



**ጥራታቸው በተጠበቀ የብረታ ብረት ምርቶቻችንና በተቀላጠፈ አገልግሎታችን ይረካሉ።**

በአዲሱ ዓመት ለደንበኞቻችን የተሻለ አገልግሎት ለመስጠት እንዲያስችል የሽያጭ አገልግሎት ቢሮ አዲስ አበባ ላይ በቅርቡ የምንከፍት መሆኑን እንገልፃለን

<u>አድራሻ</u>

ዋናው መሥሪያ ቤት
☎ 33 79 05
33 99 22
ፋክስ 33 99 47

አዲስ አበባ ካሳንቺስ አጂፕ
ፊት ለፊት
☎ 15 96 42

# የሕንፃ ዲዛይን ድርጅት



Ethiopian Embassy Office Building (Djibouti)



COMESA (former PTA) Head Office Building (Lusaka, Z.Zambia)



Customs Branch Office (Dire Dawa & Shashemene)



Addis Ababa Stadium Extension (Proposal)




BDE Head Office Address



| | | | |
|---|---|---|---|
| PBX: | 65-08-00 | Design Dept: | 65-06-28 |
| GM Office: | 65-09-60 | Cont. Admn. Dept: | 65-09-59 |
| Fax: | 65-06-17 | Mat. Testing Dept: | 65-06-13 |
| e-mail: | bde@telecom.net.et | Business Devt: | 65-06-02 |





**Major Activities**

- Building Design
- Road Design
- Water Works Design
- Contract Administration
- Supervision of Civil Work Projects
- Materials Testing

# ስብሰባ

የኤርትራው ፕሬዚዳንት አቶ ኢሳያስ አፈወርቂ በሚያራምዱት ጦረኛ ፖሊሲ ምክንያት የአፍሪካ ቀንድ ሰላም ተናግቷል:: በኤርትራና በጂቡቲ መካከል ያለው ዲፕሎማሲያዊ ግንኙነት ተቋርጧል:: በአካባቢው ያለው ፖለቲካዊ ሁኔታ እየጦዘና ወደ ማይፈለግ አቅጣጫ እየተጓዘም ይመስላል:: የዚህ መነሾ ሻዕቢያ የሚያራምደው የጦረኛነት ፖሊሲ ነው:: በሻዕቢያ የጦረኝነት ፖሊሲ ሳቢያ ከእለት እለት የሰላሙ ተስፋ እየመነመነ፤ የጦርነት አስከፊ ምስል በአካባቢው እየተጋረጠ ይስተዋላል:: በአፍሪካ ቀንድ ስላለው አጠቃላይ ሁኔታ፤ በተለይም በኢትዮጵያ፣ በኤርትራና በጂቡቲ ዙሪያ ሰፊ ቃለ ምልልስ ይዘናል:: የእፎይታ ልዩ ዘጋቢ መሀመድ ጠሐ ተወከል በቅርቡ ወደ ጂቡቲ ተጉዞ የጂቡቲ ሪፐብሊክ ፕሬዚዳንት፣ የኢጋድ ሊቀመንበርና የኢትዮጵያና የኤርትራ የአአድ ርዕሳነ ብሔራት አስታራቂ ኮሚቴ አባል የሆኑትን ፕሬዚዳንት ሐሰን ጉሌድ ኦፕቲዶንን በስፋት አነጋግሯቸዋል:: ቃለ ምልልሱ እነሆ:-

> ኢሳያስ ከአንዱ ወገን ጋር በሐሣብ በተስያዩ ቁጥር በተቃዋሚዎች መጠቀምን ይመርጣሉ:: ይህም ከጅብደኛና ጨካኝ ስብእናቸው የሚመነጭ ባሕርይ ነው
>
> ሀሰን ጉሌድ ኦብቲዶን

እፎይታ:- የኢትዮጵያንና የጂቡቲን ግንኙነት እንዴት ይመለከቱታል?

ፕሬዚዳንት ጉሌድ:- ከኢትዮጵያ ጋር ያለን ግንኙነት ከዲፕሎማሲያዊ ሽንጎ የፀዳ ነው:: የሕዝቦቻችን ግንኙነቶች በታሪካዊ ፍቅርና መጣጣም ያጌጡ ናቸው:: ከአሁኑ የኢትዮጵያ መንግስት ጋር አያሌ ስምምነቶች ተፈራርመናል:: ግንኙነታችንን ተግባራዊ ለማድረግም ብዙ ሰርተናል:: የኢትዮጵያና የጂቡቲ ግንኙነት ፖለቲካዊ፣ ማሕበራዊና ባህላዊ መሰረት ያለው ነው:: የሁለቱ ሀገራት ግንኙነት ለአካባቢው ሀገራት በአርያነት የሚጠቀስ ነው:: ከኢትዮጵያ ጋር ያለን ግንኙነት ከጥንት ጀምሮ በመልካም ሁኔታ ላይ የሚገኝ እንደመሆኑ ከኢትዮጵያ በኩል በማናቸውም ወቅት ቢሆን አደጋ ተጋርጦብን አያውቅም:: ይሁን እንጂ በደርግ ዘመን ስጋት እንደነበረብን መካድ አንሻም:: ደርግ ለአካባቢው ሕዝቦች ሁሉ የስጋት ምንጭ ነበር:: በአሁኑ ወቅት ከአቶ መለስ ዜናዊ መንግስት ጋር ያለን ግንኙነት በግልጽነትና በወንድማማችነት ላይ የተመሰረተ ነው:: ስለሆነም ነው ከኢትዮጵያ ጋር በርካታ ስምምነቶችን ለመፈራረም የበቃነው:: የወቅቱ የኢትዮጵያ መንግስት ለኢትዮጵያ ብቻ ሳይሆን ለአካባቢው ሀገራት ጭምር የሰላምና የመረጋጋት አርኢያ ሆኖ ነው የሚታየው::



የኢትዮጵያ መንግስት አካባቢውን በማረጋጋት ረገድ የሚጫወተው ሚና የሚዘነጋ አይደለም:: ኢትዮጵያ የአካባቢውን ሰላምና መረጋጋት ለማስፈን በምትሯሯጥበት ወቅት የኢሳያስ መንግስት በአካባቢው ሁከት ለመፍጠር ቢፍጨረጨርም፣ ኢትዮጵያ ዛሬም የአካባቢው ሰላምና መረጋጋት ለማስጠበቅ የምታደርገውን እገዛ እንደቀጠለች ነው:: ወደፊትም ከዚህ አቋሟ እንደማታፈገፍግ የታመነ ነው::

እፎይታ:- ኢትዮጵያንና ኤርትራን ለመሸምገል መነሳሳትዎ ይታወቃል:: ስለጉዳዩ ቢያጫውቱን?



# ፈንጂ...

> «እርግጥ ነው እኔ በባህርዬ ደመ ፍሉ ነኝ። ማንም ሰው ስሜቴን እንዲነካ አልፈቅድም። ሆኖም በዚያን ወቅት ሲቢቱን በሙሉ የኢሳያስን አነጋገር ሳወጣና ሳወርድ ያስ እንቅልፍ አንግቼ ነበር ስብሰባ አዳራሽ የገባሁት»

ፕሬዚዳንት ጉሌድ፡- እርግጥ ነው ወደ አስመራና አዲስ አበባ ለብዙ ጊዜ ተመላልሻለሁ። የዚህ ጥረት አብይ ዓላማ ችግሩ በሰላማዊ መንገድ የሚፈታበትን ዘዴ ለመሻት ነበር። ሁለቱ ሀገራት መሪዎች ጋር ተገናኝቼ ተወያይቻለሁ። የኤርትራው መሪ ሰራዊታቸውን ከኢትዮጵያ ግዛት እንዲያስወጡ ጠይቄያለሁ። ይሁንና በኢሳያስ አፈወርቂ በኩል አያሌ አስቸጋሪ ሁኔታዎች ገጥመውኛል። በቃላቸው የሚረጉ ሰው አይደሉም። ለምሳሌ ያህል አንድ ጉዳይ ለመጥቀስ ይቻላል። ኢሳያስ «ችግሩ አልቋል፣ እኔና መለስ ለጉዳዩ መፍትሔ



አግኝተንለታል፣ ጂቡቲ መጥተን ስምምነት እንፈራረማለን» አሉኝ። ከኢትዮጵያ መሪዎች ጋር ስገናኝ ደግሞ የኢሳያስ አፈወርቂ ገለፃ ትክክል እንዳልነበረ ነው የተገነዘብኩት። ኢሳያስን በተመለከተ ብዙ ምስጢር ነበረኝ። ምንያደርጋል? ለፕሬስ ፍጆታ አይሆንም እንጂ።

እፎይታ፡- ክቡር ፕሬዚዳንት ሐሰን ጉሌድ አፕቲዶን፣ ጂቡቲና ኤርትራ ውዝግብ ውስጥ የገቡበትን ምክንያት እንዴት ይገልጹታል?

ፕሬዚዳንት ጉሌድ፡- በጂቡቲና በኤርትራ መካከል የተከሰተውን አለመግባባት በበኩሌ አዲስ የተፈጠረና እየተባባሰ የመጣ ውዝግብ ነው አልልም። ኢሳያስ አፈወርቂ ሥልጣን ከተቆናጠጡ ማግሥት ጀምሮ ያለ ነገር ነው። ኢሳያስ በየወሩ አዲስ ወቀሳና ትችት ይዘው ብቅ ይሉብናል። የሩቅ ተመልካች የሆነ ወገን ጉዳዩ ዱብ ዕዳ ሊመስለው ይችል ይሆናል። በእኛ ዘንድ ግን ጉዳዩ የተለመደ ነው። ኢሳያስ ጐረቤቶቻቸውን የሚያውኩ ሰው ናቸው። ኢሳያስ ከአንዳንድ ወገኖች ጋር የመቀራረብ አዝማሚያ ሲያሳዩ ስንመለከት በሌላ ወገን ላይ ውዝግብ ለመፍጠር መዘጋጀታቸውን መጠርጠር አለብን። ይህ የኢሳያስ ልዩ ባሕርይ ነው። ሰውዬው ከውዝግብ ውጭ መኖር የሚችሉ ሰው አይደሉም።

እፎይታ፡- ይህን ማለት እናንተ ገለልተኛ አቋማችሁን በመለወጥ ከኤርትራ ጋር ትንቅንቅ ውስጥ መግባታችሁ ይሆን?

ፕሬዚዳንት ጉሌድ፡- እያዘንኩ አንድ ነገር ለመናገር እፈልጋለሁ። ኢሳያስ ኤርትራን በመምራት ያሳለፏቸውን ሰባት ዓመታት ስንገመግም የምናገኘው ውጤት የሥርዓቱ ገላጭ ባሕርያት አለመረጋጋትን መፍጠር መሆኑን ብቻ ነው። ኢሳያስ አፈወርቂ ከሚመሩት መንግሥት ጋር መቻቻል ይቻላል የሚለው ተስፋችን ተሟጦጧል። ከፊታችን የተደቀነው አማራጭ ኢሳያስ ከሚመሩት መንግሥት ጋር አለመሥራት ሆኖ ተገኝቷል።

እፎይታ፡- ከኤርትራ ጋር ያላችሁን ግንኙነት ታቋርጣላችሁ ማለት ነው?

ፕሬዚዳንት ጉሌድ፡- እኔ ያልኩት ከኢሳያስ ጋር ያለን ግንኙነት ይቋረጣል ነው። ከኤርትራ ምድርና ሕዝብ ጋር ያለንን ግንኙነት ግን ማቋረጥ አንችልም። ከሕዝቡ ጋር ያለንን ግንኙነት የማቋረጥ እቅድ የለንም። አንደኛ ነገር በሁለቱ ሀገራት መካከል ጂዮግራፊያዊ ግንኙነት አለ። በሕዝቦቻችን መካከልም ልዩ የሆነ ግንኙነት አለ። በኢሳያስ አፈወርቂ ድርጊት ምክንያት ከተውነም ሊነካ የሚገባው ግንኙነት አይደለም። ኢሳያስ አፈወርቂ የኤርትራን ሕዝብ ከክልሉ ለማግለል እየጣሩ ነው። በእርግጥም የኤርትራን ሕዝብ ከዓረባዊና አፍሪካዊ ክልሉ በማግለል ረገድ ተሳክቶላቸዋል ለማለት ይቻላል። እኛ የኤርትራን ሕዝብ በጥልቀት ከሚያውቁት ሁሉ በላይ እናውቀዋለን። ሕዝቡን አምባገነናዊ ሥርዓት ተጭኖታል። በእንቅርት ላይ ጆሮ ደግፍ እንዲሉ በኤርትራ ሕዝብ ላይ መረባረብ ያለብን አይመስለኝም።

እፎይታ፡- ኤርትራ በጂቡቲ የመደበቻቸውን አምባሳደር ሚና (ጄነራል ከመሆናቸው አንፃር) እንዴት ይመለከቱታል?

ፕሬዚዳንት ጉሌድ፡- እኛ በአምባሳደሩ ላይ ከአቅማቸው በላይ የሆነ ጫና መፍጠር አንሻም። የአምባሰደሩን ሹመት በመሠረቱ የተቀበልነው ጉዳይ ነው። ሹመታቸውም ቢሆን ከሀገራቸው ሉዓላዊነት አኳያ የሚታሰብ የሀገሪቱ የውስጥ ጉዳይ ስለሆነ ጣልቃ መግባት አይቻለንም። ሆኖም ከሰውዬው ሹመት ጋር የተያያዘና ሁለቱን ሕዝቦቻችንን የሚያናቁር ሁኔታ ሳይፈጥር የሚቀር አይመስለኝም። በግል አስተያየቴ የነገሮቹ ዕድገት ከኢሳያስ ፍላጎትና ተለዋዋጭ ስብእና ጋር በቀጥታ የተያያዘ ይመስለኛል።

እፎይታ፡- ዲፕሎማሲያዊ ግንኙነታችሁን የማቀዝቀዝ አዝማሚያ አለ?

ፕሬዚዳንት ጉሌድ፡- እኛ በመሠረቱ በመቀራረጥ ፖሊሲ አናምንም ነበር። በተለይም እንደ ኤርትራና ጂቡቲ እጅግ ጥልቀት ባለው ወንድማዊ ትሥሥር በተቆራኙ ሕዝቦች መካከል ያለውን የግንኙነት ሰንሰለት መበጠስ አንፈልግም ነበር። እያዘንን የኢሳያስ አፈወርቂ የመገለባበጥ ባሕርይን

ለመጋፈጥ ተገደናል። በዚህም የተነሳ ፖለቲካዊ እርምጃዎችን ወስደናል። አሥመራ የሚገኘውን አምባሳደራችንን ወደ ጂቡቲ ጠርተናል። በአስመራ የነበረውን ኤምባሲያችንንም ዘግተናል። እኛ የሰከነ አመራር ከሌለው መንግሥት ጋር መስራት ያዳግተናል። አቶ ኢሳያስ የጂቡቲን ክብር አዋርደዋል፣ የሀገሪቱን ርዕሰ ብሔር ዘልፈዋል። ስለሆነም ከኤርትራ መንግሥት ጋር ዲፕሎማሲያዊ ግንኙነት መቀጠሉ ፋይዳ የለውም። በዚህም ምክንያት ከኤርትራ መንግሥት ጋር ያለንን ዲፕሎማሲያዊ ግንኙነት ሙሉ ለሙሉ አቋርጠናል።

**እፎይታ፦ ዘገቶችን ከአንዱ ሀገር ወደ ሌላው የማባረሩ ዘመቻ በጂቡቲ ይጀመር ይሆን?**

ፕሬዚዳንት ጉሌድ፦ በጂቡቲ ውስጥ በሚኖሩ ኤርትራውያን ላይ አንዳችም ጉዳት እንደማይደርስ ላረጋግጥ እወዳለሁ። ጂቡቲ በቅኝ አገዛዝ ሥር ከነበረችበት ወቅት ጀምሮ በርካታ ኤርትራውያን በጂቡቲ ይኖራሉ። ከጂቡቲ ሕዝብ ጋር ተጋብተው፣ ተዋልደው፣ አብረውን ይኖራሉ። የሕዝባችንን ደስታውንም፣ ሐዘኑንም ይጋራሉ። አንዳችም ነውር አላየንባቸውም። ስለሆነም ከኢሳያስ ጋር ባለን አለመግባባት ሳቢያ አንዳችም ጉዳት በኤርትራውያን ላይ እንዲደርስ አንፈቅድም። ኢሳያስ አፈወርቂ በኤርትራ ሕዝብና በሱዳን ሕዝብ መካከል ጥላቻ ያለን ለማስመሰል የሚጥሩትን ያህል፣ በኤርትራ ሕዝብና በጂቡቲ ሕዝብ መካከል፣ በኤርትራ ሕዝብና በኢትዮጵያ ሕዝብ መካከል ጠብ ያለ ለማስመሰል ሲሯሯጡ ይታያሉ። ልዩነት ያለው በፕሬዚዳንት ኢሳያስና በአካባቢው መንግሥታት መካከል እንጂ በሕዝቦች መካከል አይደለም። እኔ በዚህ ረገድ ከአካባቢያችን ልምድ በመነሣት የኤርትራን ሕዝብ ስሜት ጠንቅቄ አውቀዋለሁ ለማለት እደፍራለሁ። የኤርትራ ህዝብ ማንም በማይመኘውና በማይፈልገው አጣብቂኝ ውስጥ ገብቷል። ኢሳያስ አፈወርቂ የኤርትራን ሕዝብ ከዓረባዊና አፍሪካዊ አካባቢው በማግለል ረገድ በእጅጉ ተሳክቶላቸዋል። ስለሆነም እኛ ኢሳያስ በአጠመዱብን ወጥመድ ውስጥ ላለመግባት መጠንቀቅ ይኖርብናል። ያን ካደረግን በኢሳያስ ሐጢያት ምክንያት የሚከሰሰውና የሚቀጣው ሕዝብ ኢሳያስን በጉያው እንዲያቅፍ እናስገድደዋለን ማለት ነው።

**እፎይታ፦ ከኢሳያስ ጋር ባላችሁ ቅራኔ የተነሳ የኤርትራን ተቃዋሚ ኃይላት ታቅፋላችሁ ማለት ነው?**

ፕሬዚዳንት ጉሌድ፦ እኛ ከኢሳያስ ጋር ተለያይተናል። ይህ እርግጥ ነው። ስርዓቱን የመለወጥ ጉዳይ ግን የኤርትራ ሕዝብ ብቸኛ መብት ነው። በኤርትራ ሕዝብ ጉዳይ ጣልቃ አንገባም፣ በፍጹም። በተቃዋሚዎች መጠቀም ከመርሖአችን ጋር የሚጣጣም ፖሊሲ አይደለም።



**ኢሳያስ አፈወርቂ ከስብሰባው አዳራሽ እንደገቡ በመጀመሪያ ጊዜ የተነፈሱት ቃል ቢኖር በጣታቸው ወደኔ እያመለከቱ እዚህ ኢትዮጵያዊ ፊት አልናገርም የሚል ነበር**



**እፎይታ፦ በአንዳንድ የጂቡቲ ምንጮች ዘገባ መሠረት ኤርትራ የጂቡቲ ተቃዋሚዎች የሚሰለጥኑባት ካምፕ መሥርታለች። እውነት ነው?**

ፕሬዚዳንት ጉሌድ፦ ይህ የፕሬዚዳንት ኢሳያስ አፈወርቂ ቋሚ መርሕ ነው። ስለሆነም ሊያስደንቅና ጉድ ሊያሰኝ አይገባም። ኢሳያስ ከአንዱ ወገን ጋር በሐሣብ በተለያዩ ቁጥር በተቃዋሚዎች መጠቀምን ይመርጣሉ። ይህም ከጅብደኛና ጨካኝ ስብእናቸው የሚመነጭ ባሕርይ ነው። አመለካከታቸው ከጠባብ፣ ከኃይልና ከጭካኔ ዙሪያ ርቆ የማይጓዝ ነው። በእጅጉ የሚያሳዝነው ኢሳያስ በአለፉት ሰባት ዓመታት ያፈሩት ምርት ቢኖር የኤርትራን የተገለለ መንግሥት መፍጠር ብቻ ነው። በበኩላችን ኢሳያስ ተቃዋሚዎቹንም ሆነ ሌሎችን መደገፋቸው እኛን አያሸብረንም።

እኛ ለጂቡቲያውያን ዴሞክራሲያዊ ሕይወት አመቺ ሁኔታ ፈጥረናል። የሕዝባችን መሠረታዊ መብቶች በሕግ ተረጋግጠውላቸዋል። ኢሳያስ ግን የኤርትራን ሕዝብ በእሳትና በጠመንጃ አፈሙዝ አስገድደው መግዛታቸው ለማንም የተሰወረ አይደለም። እኛ በጂቡቲያውያን መካከል የሥልጣንና የሀብት ክፍፍልን ፍትሐዊነትና የሕግን የበላይነት በዴሞክራሲያዊ መርሕ አኳያ እንዲረጋገጡለት ያደረግን ስለሆነ ኢሳያስ አፈወርቂ የሚያስታጥቁትን ጠመንጃ በሀገሩ ላይ ሊያነጣጥር የሚቃጣ ጂቡቲያዊ መገኘቱን እጠራጠራለሁ። በሺ የሚቆጠሩ ዜጐቻቸውን በእሥር ቤት ያጐሩት ሥልጣንና ሀገራዊ ሀብቱን በሞኖፖል የሚቆጣጠሩት ኢሳያስ፣ ማናቸውንም የአፍሪካ ቀንድ ሀገራትን ዜጋ ጠመንጃ አንግቦ በሀገሩ ላይ ጥቃት እንዲሰነዝር ለማሳመን የሚያስችል ተቀባይነት ይኖራቸዋል ተብሎ በፍፁም አይታሰብም። የጂቡቲን ተቃዋሚዎች በተመለከተ በመካከላችን የጋራ አመለካከት መኖሩን ማረጋገጥ እሻለሁ። ተቃዋሚዎችም እንደኛው ኢሳያስ አፈወርቂ ለአካባቢው ሠላምና መረጋጋት ጠንቅ መሆናቸውን ያምናሉ። ማናቸውም ጂቡቲያዊ ኢሳያስ አፈወርቂ በተደጋጋሚ በጂቡቲ ላይ ያነጣጠሩትን ዘለፋና ውርደት ከቶውንም አይረሳውም። ይህን በተመለከተ ለምሳሌ ያህል አንድ ትዝታ ማውሳት እሻለሁ። ኢሳያስ አፈወርቂ ብዙ ጊዜ የጂቡቲን ዓረባዊነት በማቃለል ይናገራሉ። ስለኤርትራ ዓረባዊነት በተጠየቁ ቁጥር «ጂቡቲ ዓረብ ከሆነች እኛ ኤርትራውያን ይበልጥ ዓረቦች ነን ማለት ነው» ይላሉ።

«ኤርትራ ራሷን የቻለች መንግሥት ለመሆን የሚያበቃት ኢኮኖሚያዊ አቅም የላትም» የሚል አስተያየት የቀረበላቸው እንደሆን አቶ ኢሳያስ ጣታቸውን ወደኛ ይቀሥራሉ «ጂቡቲ አለችላችሁ አይደል፤ በዕርዳታና በምጽዋት ኢኮኖሚ የቆመች» በማለት

ሀገራችንን ያኳስሳሉ::

የኤርትራ ነፃነት በተከበረበት ዕለት ከዓረብ ሀገራት መሪዎች መካከል እኔና የሱዳኑ ፕሬዚዳንት አልበሺር ብቻ መገኘታችን እየታወቀ ፕሬዚዳንት ኢሳያስ አፈወርቂ የኢትዮጵያ ወኪሎች ናችሁ በማለት ሲከሱን ከርመዋል:: ይህ በአንድ የጅቡቲ ዜጋ በሆነ ሰው ላይ ያነጣጠረ ስድብ ሳይሆን የመላውን የጅቡቲ ሕዝብ ሕሊና የሚያደማ ከፍተኛ ውርደት ነው:: ኢሳያስ የጠላትነት መንፈስ የፈጠሩት ከጅቡቲ ሕዝብ ጋር ብቻ ሳይሆን ከመላው የዓረብ ሕዝብ ጋር ነው:: ስለሆነም ከኢሳያስ አፈወርቂ ጋር ለመስራት የሚሻ ማናቸውም ተቃዋሚ ፖለቲከኛ ፖለቲካዊ ሕይወቱን አጣብቂኝ ውስጥ ለመክተት የሚሻ ብቻ ነው::

**እፎይታ:- በእርስዎ ግምት ፕሬዚዳንት ኢሳያስ ጅቡቲ ከአአድ አስታራቂ ቡድን እንድትወጣ የጠየቁት ለምን ደመስሎታል?**

ፕሬዚዳንት ጉሌድ:- ይህንን መመለስ ያለባቸው ኢሳያስ አፈወርቂ ብቻ ናቸው፤ ይሁን እንጂ አስታራቂው ቡድን ይህን ጉዳይ ከሁለት ነገሮች ጋር ያያይዘዋል:: ኢሳያስ ሁለት ግቦች ማረጋገጥ ይሻሉ:: አንደኛው ዓላማ አዲስና ያልታሰበ ጉዳይ ፈጥሮ እንግዳ ስሜት ማስፈን ነው:: ሁለተኛው ዓላማ አስታራቂው ቡድን ያሳለፈውን ውሳኔ ላለመቀበል ማምለጫና መሸሎኪያ መንገድ ለመቅደድ የታለመ ነው:: ይህንን ተንኮል አስታራቂ ቡድኑ ደርሶበታል:: ኮሚቴው የውይይቱን ሒደት ከስሩ ለማፍረስ ኢሳያስ የሚያደርጉትን ጥረት ለማክሸፍ ጥሯል:: በተለይ በእኔ ላይ ያነጣጠረውን አሉታዊ ዘመቻ በተቻለ መጠን በትዕግስት እንዳስታምምና ለአምስት ተከታታይ ወራት የዘለቀው የአስታራቂነት ጥረት እንዳይደናቀፍ ኮሚቴው በአግባባኝ መሰረት መቻቻልን መረጥሁ::

ፕሬዚዳንት ኢሳያስም በኮሚቴው ሐሳብ ላይ ብቻ አስተያየታቸውን እንዲሰጡ ተነገራቸው:: ጅቡቲን ከኮሚቴው አባልነት የማስወጣቱ ስልጣን የኮሚቴው ድርሻ እንዳልሆነም እንዲያውቁት ጥረት ተደርጓል:: ኮሚቴው በተቻለው አቅምና ዘዴ በኢሳያስ ላይ ተጽእኖ በማድረግ በመጨረሻ የኮሚቴው ስብሰባ ላይ እንዲገኙ ለማስገደድ ተችሏል::

**እፎይታ:- ጅቡቲ ከኮሚቴው እንድትወጣ የሚጠይቀውን የኤርትራን ጥያቄ መቼና እንዴት ሰሙ?**

ፕሬዚዳንት ጉሌድ:- የዚምባብዌውን ፕሬዚዳንት ሮበርት ሙጋቤንና የቡርኪና ፋሶው ፕሬዚዳንት ብሌይዝ ካምፓኦሬንና ኢሳያስን ጨምሮ እኔ በሌለሁበት ስድስት ሰዓታት የፈጀ ስብሰባ ሲያደርጉ አንድ ነገር ውስጤን ተሰማው:: ኢሳያስ አፈወርቂ አዲስ ዱብ ዕዳ ይዘው ብቅ እንደሚሉ ብጠረጥርም፣ በማናቸውም መለኪያ ቢሆን እኔን ይወነጅላሉ የሚል ስሜት አልነበረኝም::

**እፎይታ:- ጉዳዩ እንዴት ተነገርዎት? እንዴትስ ተቀበሉት?**

ፕሬዚዳንት ጉሌድ:- ከጂቡቲ ልዑካን ቡድን ስሜት ኢሳያስ አፈወርቂ ስብእናዬንና ጂቡቲን መዝለፋቸውን ተረዳሁ:: ፕሬዚዳንት ሙጋቤም የኢሳያስን ጥያቄ በዝርዝር ከነገሩኝ በኋላ ጥያቄው ውድቅ መሆኑን ጭምር ገለፁልኝ:: መልስ ለመስጠት እንዳልቃጣና ለጥረቱ መናጋት ምክንያት እንዳልሆን ሙጋቤ አግባቡኝ:: ሆኖም ዝግ ስብሰባ እንዲዘጋጅልንና ለኢሳያስ አፈወርቂ መሰረተ ቢስ ክስ መልስ እንድሰጥ ጠየቅሁ:: ጥያቄዬ በኮሚቴው በኩል ተቀባይነት ሲያገኝ ኢሳያስ አፈወርቂ ግን አሻፈረኝ አሉ:: እንድያውም አቶ ኢሳያስ ከኢትዮጵያውያን ጋር ፊት ለፊት ተገናኝቼ ለመወያየት ዝግጁ ነኝ፣ ከጂቡቲው ቡድን ጋር ለመነጋገር ግን ዝግጁ አይደለሁም በማለት ተናግረዋል::

**እፎይታ:- የኢሳያስን ዘለፋ፣ እንዴት መቋቋም ቻሉ?**

ፕሬዚዳንት ጉሌድ:- እርግጥ ነው እኔ በባህርዬ ደመ ፍሉ ነኝ:: ማንም ሰው ስሜቴን እንዲነካ አልፈቅድም:: ሆኖም በዚያን ወቅት ሌሊቱን በሙሉ የኢሳያስን አነጋገር ሳወጣና ሳወርድ ያለ እንቅልፍ አንግቼ ነበር ስብሰባ አዳራሽ የገባሁት:: በ1992፣1993 እጅግ አሳሳቢ የሆነ የጤና መታወክ አጋጥሞኝ በነበረበት ወቅት ኢሳያስ አፈወርቂ ሆን ብለው እኔን ለማናደድና ለባሰ የጤና መታወክ ለመዳረግ ሕሊናዬን በሚያደሙ ቃላት ሲወርፉኝ ነበር:: ሰውዬው የጤንነቴን ሁኔታ ይከታተላሉ:: የልብ ድካሜን በማባባስ ሕይወቴን ለአደጋ ማጋለጥና ለፖለቲካዊ ፋይዳ የሚረዳ ቀውስ ጂቡቲ ውስጥ የመፍጠር አደገኛ የፖለቲካ ቁማር ይጫወቱ ነበር:: ከኔ ሕልፈት በኋላ ኢሳያስ የፖለቲካ ክፍተትና ስርዓት አልበኝነት እንዲስፋፋ በማድረግ ድፍርስ ውሃ ውስጥ ዓሣ ማጥመድ መሻታቸውን የቀድሞ ትዝታዎቼ ስላስገነዘቡኝ የኢሳያስን ድንፋታ በትዕግስትና በለስላሳ አእምሮ ማስታመም ነበረብኝ:: ኢሳያስ የጠበቁትን አጋጣሚ በዚህ መልክ ነፈግኋቸው:: ኢሳያስ አፈወርቂ ከስብሰባው አዳራሽ እንደገቡ በመጀመሪያ ጊዜ የተነፈሱት ቃል ቢኖር በጣታቸው ወደኔ እያመለከቱ «እዚህ ኢትዮጵያዊ ፊት አልናገርም» የሚል ነበር:: እኔ በአቅራቢያቸው የተቀመጥኩ ብሆንም አንዲት ቃል አልተነፈስኩም:: ኢሳያስ በመቀጠልም «ጂቡቲ ውሳኔዎቹን ፖለቲካዊ ቅባት በመቀባት ለኢትዮጵያ እንዲያገለግሉ በማድረግ ላይ ነች» ሲሉ ተናገሩ::

«በዚህን ጊዜ ንግግሩን ወደ ኮሚቴው ሊቀመንበር እንዲያመራ ይሁን፣ እኔ ርዕሰ ብሔር ነኝ» በማለት መለስኩ:: በስብሰባው አዳራሽ የተለዋወጥናቸውን እንኳ ሰላንቲያዎች ለአንባብያን መግለጹ አስፈላጊ አይመስለኝም::

በኮሚቴው በኩል ገና ብዙ ያልተጠናቀቁ ስራዎች አሉ:: ስለነዚህ ጉዳዮች በአሁኑ ወቅት መግለጫ መስጠት ማለት ችግሩን በሰላማዊ መንገድ ለመፍታት የሚደረገውን ጥረት ማደናቀፍ ይሆናል:: የኤርትራ ፕሬዚዳንት ግን እንዳሻቸው መናገር ይችላሉ:: ከዚህ ቀደም ናይሮቢ ላይ በዝግ ስብሰባ ውይይት የተካሔደበትን ጉዳይ ይፋ አውጥተዋል:: በእርሳቸውና በአልበሺር መካከል ስለተደረገው እንኳ ሰላንቲያም ለጋዜጠኞች አውርተዋል:: ጋዜጦችም እንደዘገቧቸው ተመልክታችኋል::

በእሳቸውና በመለስ ዜናዊ መካከል በግል ስለተደረጉት የደብዳቤ ልውውጦችም አውርተዋል:: ርዕሰ ብሔርተኛነታችን እንዳሻን እንዳንናገር የሚያደርገን ፕሮቶኮል መኖሩን ኢሳያስ አይገነዘቡም:: በርዕሰ ብሔርነት ዙሪያ ልዩ ማነቀ አለ:: ርዕሰ ብሔር ንግግሩም፣ እንቅስቃሴውም፣ ግንኙነቱም፣ ውሱንና ጥብቅ ነው:: ኢሳያስ ከዚህ ሐቅ ጋር እምብዛም አይጣጣሙም::

**እፎይታ:- አንዳንድ የወሬ ምንጮች እንደሚሉት ከሆነ የኤርትራ ባለስልጣኖች ከአንዳንድ የጅቡቲ ባለስልጣኖች ጋር መግባባት አለመቻላቸውን በተደጋጋሚ ለእርስዎ መግለፃቸውን የኤርትራው የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር መስከረም ሳይ ጂቡቲን በጎበኙበት ወቅት ይህንኑ እንደገ ለጹልዎ ይናገራሉ:: ይህ ምን ያህል እውነት ነው?**

ፕሬዚዳንት ጉሌድ:- የኤርትራው ፕሬዚዳንት ኢሳያስ ምንጊዜም

በየሀገራቱ መዋቅሮች ውስጥ ጉድለቶችና ክፍተቶች መኖራቸውን ለማሳየት ይሞክራሉ:: ስለሆነም ከራሳቸው እይታ በመነሳት በሱዳን፣ በየመን፣ በኢትዮጵያና በመጨረሻም በጂቡቲ ያሉትን ስርዓታት መገምገም ይሻሉ:: በጂቡቲ የውሳኔ ምንጭ አንድ ወጥና የተዋሐደ ነው::

ኢሳያስ እንደሚሉት በመንግስት መዋቅር ውስጥ ልዩነትና አለመግባባት የለም:: ውሳኔዎች የሚተላለፉት በሕግ አውጪና በሕግ አስፈፃሚ አካላት ምክክር ከተደረገባቸው በኋላ ብቻ ነው:: ኢሳያስ ግን ድፍርስ ውሃ ውስጥ ዓሣ ማጥመድ አማራቸውና በአንዳንድ የአካባቢው ሀገራት ውስጥ ባለው አለመግባባት ቅኝት በመታገዝ ጂቡቲ ውስጥ ሁከት መፍጠር ፈለጉ:: አልተሳካላቸውም:: ለኔ ለግሌ ቀደም ሲል ኢሳያስ አንዳንድ የጂቡቲን ባለስልጣናት በማሳጣት የተለያዩ ደብዳቤዎችን ጽፈውልኝ ነበር::

በባለስልጣናቱ ላይ የሚሰነዝሩት ውንጀላ የጂቡቲ መንግስት ባለስልጣናት ለኢትዮጵያ ጥቅም ያገለግላሉ የሚል ነበር:: በእኔ ግምት የኤርትራው ፕሬዚዳንት እጅግ ውስብስብና ደቋሽ የውስጥ ችግር አረንቋ ውስጥ ገብተዋል::

**እፎይታ:-** ኤርትራውያን በእርስዎ ላይ ከሚሰነዝሩት አስተያየት መካከል ሁሌም በሌሎች ሐሳብ እንደሚመሩና ለኢትዮጵያ ሉዓላዊነት መከበር ይረዳ ዘንድ በገንዘብ የተገዛ ድጋፍ እንደምታደርጉ፣ ነው:: በዚህ ጉዳይ ላይ አስተያየትዎን ቢሰጡኝ?

**ፕሬዚዳንት ጉሌድ:-** ትልቁ ችግር የኤርትራው ስርዓት ገለልተኝነት የሚሰኝ መርሕ መኖሩን ፈጽሞ መገንዘብ አለመቻል ነው:: ቀደም ሲል የተዘጋጀ ውሳኔ ያሳልፍብኃል:: ከጐኑ ካልቆምክ ከመቅጽበት በተቃራኒው ጐራ ያሰልፍሀል:: ትልቁ ችግር ያ ነው::

**እፎይታ:-** በአብዛኛው አቋማችሁ ከኢትዮጵያ ጐን የሚያሰልፋችሁ ነው የሚል ግምት ያላቸው ታዛቢዎች አልጠፉም:: ስለዚህ አስተያየት ምን ይላሉ?

**ፕሬዚዳንት ጉሌድ:-** ይህ ትክክል አይደለም:: እኛ ከማንም ጋር አልወገንም:: በማናቸውም አጋጣሚ የኤርትራን ሕዝብ ጥቅም አልተፃረርንም:: የጂቡቲ፣ የኢትዮጵያና የኤርትራ ሕዝቦች ከአንድ ምንጭ የተቀዱ ወንድማማች ሕዝቦች ናቸው:: እኛ የምንቃረነው ዘልዓለማዊ ካልሆነው ከኤርትራ መንግስት ጋር ብቻ ነው፤ እንጂ ከኤርትራ ሕዝብ ጋር አይደለም:: ከኢትዮጵያ ጋር የጋራ የኢኮኖሚ ጥቅሞች ያሉን መሆኑ እየታወቀ ኢትዮጵያ በኤርትራ ላይ የዓየር በረራ ክልከላ በአወጀችበት ወቅት ኢሳያስ ስልክ ደውለው የአየር በረራውን እንዳላቋርጥ በጠየቁን መሰረት የምግብ ሸቀጣሸቀጥ ወደ አስመራ እንዲሻገርና የዓየር በረራውም እንዲቀጥል አድርገናል:: በወቅቱ አስመራን ከውጭው ዓለም የምናገናኘው እኛ ብቻ ነበርን::

የኤርትራንም ነፃነት ተቃውማችኋል የሚለውም ውንጀላ መሰረተ ቢስ ነው:: እኛ የአካባቢው ሕዝቦችን የነፃነት ፍላጐት የታቀረንበት ወቅት በፍጹም የለም::

> « *የኤርትራ ህዝብ ማንም በማይመኘውና በማይፈልገው አጣብቂኝ ውስጥ ገብቷል:: ኢሳያስ አፈወርቂ የኤርትራን ሕዝብ ከዓረባዊና አፍሪካዊ አካባቢው በማግለል ረገድ በእጅጉ ተሳክቶላቸዋል:: ስለሆነም እኛ ኢሳያስ በአጠመዱብን ወጥመድ ውስጥ ሳንገባት መጠንቀቅ ይኖርብናል* »

**እፎይታ:-** በቅርቡ በኢትዮጵያና በጅቡቲ ድምበር አቅራቢያ በነዳጅ ጫኝ ተሽከርካሪዎች ላይ አደጋ መድረሱና ጥቂት መኪናዎች መቃጠላቸው ተሠምቷል፣ አደጋውን ያደረሱትም ከኤርትራ የተነሱ የጂቡቲ ተቃዋሚዎች ናቸው ተብሏል:: ምን ያህል እውነት ነው?

**ፕሬዚዳንት ጉሌድ:-** በቅርቡ እንደሰማነው ከሆነ ኢሳያስ አንዳንድ ተቃዋሚ ተበዮዎችን እያሰባሰቡ ነው:: ሊደረሰው ጥፋት ሐላፊነት ተሸካሚው ራሳቸው ይሆናሉ:: በበኩላችን አስፈላጊውን የመከላከል ቅድመ ዝግጁነትን አድርገናል:: ማናቸውንም የጠላትነት ትንኮሳ ለመመከት ተዘጋጅተናል:: መከላከያ ኃይላችን የጂቡቲን ሰላምና ሉዓላዊነት ለማስከበር የሚያስችለንን እርምጃ ሁሉ እንዲወስድ ታዟል:: የጦር ኃይላችን ከፍተኛ ታጋሽነትን በማሳየትና ስሜትን በመቆጣጠር ስልት በመጠቀም ለኤርትራ የጠብ አጫሪነት ትንኮሳ አጸፋ እንዳይመልስም ታዟል:: ኤርትራውያን ወደሚፈልጉት ወታደራዊ ትንቅንቅ ላለመግባት ጥንቃቄ ይደረጋል:: በኤርትራ ድምበር አቅራቢያ የሚኖሩ ዜጐቻችንም አካባቢውን ለቀው እንዲወጡ አድርገናል:: በመኪኖቹ ላይ ስለደረሰው ጥቃት ተጠያቂ የሆነውን ወገን ለማመልከት ጊዜው ገና ይመስለኛል:: በግምት መናገር አይቻለኝም:: ሁኔታው ወደ አንድ አቅጣጫ የሚያመራ ለመሆኑ ጥርጣሬ አለ:: አንዳንድ ወገኖች ወንጀለኞቹ ከኤርትራ የመጡ አፋርኛ ተናጋሪዎች ናቸው ቢሉም ይህ አንድን ወገን ለመወንጀል የሚያበቃ ማስረጃ ሊሆን አይችልም:: ወንጀሉን የማጣራቱ ሥራ ግን ቀጥሏል:: ምርመራው ሲጠናቀቅ ወንጀለኞችን በዓለም አቀፍ ሽብር ፈጣሪነት እንፋረዳቸዋለን::

**እፎይታ:-** የመን ኤርትራ ከኢትዮጵያና ከጂቡቲ ጋር ያላትን አለመግባባት ለመሸምገል ጥረት መጀመሯ ተደምጧል:: ስለሁኔታው ቢያብራሩልን?

**ፕሬዚዳንት ጉሌድ:-** ዜናውን በመገናኛ ብዙሐን አማካኝነት ሰምተነዋል:: የየመን ሕዝብና መንግሥት ስለ ኢሳያስ ባሕርይ የጠለቀ ዕውቀት አላቸው:: በአንድ ወቅት የኢሳያስ መንግሥት በሐኒሽ ላይ ድንገተኛ ወረራ ፈጽሞባቸዋል:: ዓለም አቀፉ ውሳኔ የሐኒሽ ደሴቶች የየመን ግዛት መሆናቸውን ማረጋገጡ በእጅጉ አስደስቶኛል:: ጂቡቲ በወቅቱ ከየመን ጐን ቆማለች:: የኤርትራ መንግሥት በጂቡቲ ላይ መጠነ ሰፊ የሆነ የተንኮል ድር እንዲያደራ ምክንያት የሆነው አንዱና መሠረታዊው ምክንያት ይኼው አቋማችን ይመስለኛል:: ሚያዝያ 96 ላይ ኤርትራ በባብኤልመንደብ ትይዩ በምትገኘው ዱሜራ በተሰኘችው የጂቡቲ አካባቢ ላይ አደጋ ለመጣል ቃጥታለች:: በጂቡቲ ላይ ተፅእኖ ለማሳደር በአለመ መልኩ የኤርትራ መንግሥት ዱሜራን በኤርትራ ግዛት ውስጥ የሚያካትት ካርታ አሳትሟል:: ከዚያ በኋላ ኤርትራውያን ካርታው በስዊስ መንግሥት የተሰጠ ስጦታ

መሆኑንና «ኦፊሴላዊ» ግምት ሊሰጠው እንደሚገባ አስታወቁ:: በበኩላችን ካርታዎች በስጦታ መልክ እንደማይቀርቡ እናውቃለን:: ባብ.ኤልመንደብን ለመቆጣጠር ካላቸው ዓላማ የመነጨ መሆኑ አልጠፋንም ነበር:: ዋናው ቁም ነገር የሐኒሽ ደሴቶች ውሳኔው ለየመን መሆኑ በጀ እንጂ ውሳኔው ለኤርትራ ያደላ ቢሆን ኖሮ አካባቢው መጨረሻ ወደሌለው ትርምስ ያመራ እንደነበር አይጠረጠርም::

ከየመን ጋር ያለን ግንኙነት ፍጹም ወንድማዊ ነው:: ከአሊ አብደላ ሳላሕ ጋር ቀጥተኛ ግንኙነት አለኝ:: በቅርቡ የየመኑ ጠቅላይ ሚኒስትር አብዱል ከሪም አልኢርያኒ ጐብኝተውን ነበር:: በዚህም ወቅት ከፍተኛ የጋራ ኮሚሽን የሚመሠረትበትን ስምምነት አፅድቀናል:: በሁሉም መስክ ያለን ግንኙነት በእጅጉ መልካምና የሰመረ ነው:: የኤርትራንና የየመንን ግንኙነት በተመለከተ ጉዳዩ ጂቡቲን አይመለከትም:: ሆኖም የመኖች ስለኢሳያስ ተለዋዋጭ ባሕርይ አሳምረው ስለሚያውቁ እንደኔ ግምት በእኛና በኤርትራ መካከል ያለውን አለመጣጣም ለመሸምገል ይነሳሳሉ የሚል ግምት የለኝም:: በመሠረቱ የጠቡ መነሾ በሐኒሽ ጉዳይ ላይ ከየመን ጐን መቆማችን ነው:: ኤርትራና ኢትዮጵያን በተመለከተ ኢሳያስ ኢትዮጵያንና የመንን ለማቃቃር ይጥሩ ይሆናል:: ወይም ጂቡቲንና የመንን ለማናቆር ይነሳሱ ይሆናል:: ያም ሆኖ እንደ እኔ እምነት ኢሳያስ በየመንና በአፍሪካ ቀንድ መካከል፣ ውዝግብ እንዲፈጠር ማድረግ የሚችሉ አይመስለኝም:: የመኖች ቀደም ሲል እንዳልኩት የኢሳያስን የጠብ አጫሪነት ፖሊሲ ጠንቅቀው ስለሚያውቁ በዚህ ጉዳይ ላይ እምብዛም ይጨነቃሉ አልልም:: የችግሩ አፈታት የተያዘው በአፍሪካ አንድነት ድርጅት ነው:: ኢሳያስ አንዳንድ የአረብ ሀገራት ለችግሩ መፍትሔ በማፈላለግ ረገድ ተካፋይ እንዲሆኑ ቢማፀኑም ያገኙት መልስ በዚያው በተጀመረበት አፍሪካዊ መድረክ ይለቅ የሚል ነው:: ሌላ የአስታራቂነት ሃሳብ አለኝ የሚል ወገን ሁሉ ትክክለኛውን አቅጣጫ እየሳተ መሆኑን ሊገነዘብ ይገባል እንላለን::

ጅቡቲንና ኤርትራን በተመለከተ ግን መሸምገል የሚያስፈልግ አይመስለኝም:: ኢሳያስ የስም ማጥፋት ዘመቻ እያካሔዱብን ስለሆነ በሳቸው ላይ ያለንን አቋም የመወሰኑን ሒደት ማዘግየት ተገደናል::

እፎይታ:- ክቡር ፕሬዚዳንት፣ አረቦች ከኤርትራ ጋር ያሰቸውን ግንኙነት ለማሻሻል እየጣሩ ነው ይባላል:: ይህን እንዴት ይመለከቱታል?

ፕሬዚዳንት ጉሌድ:- በዚህ ረገድ የተቀየረ አቋም መኖሩን እጠራጠራለሁ:: ኢሳያስ ያው አረቦች የሚያውቋቸው ኢሳያስ ናቸው::

የሐኒሽን ደሴቶች ለየመን የመለሰላቸው ዓለም አቀፉ ፍርድ ቤት እንደሆነ ግልጽ ነው:: ውሳኔው ከተሰጠም በኋላ አቶ ኢሳያስ

> **ማናቸውንም የጠላትነት ትንኮሳ ለመመከት ተዘጋጅተናል:: መከላከያ ኃይላችን የጂቡቲን ሰላምና ሉዓላዊነት ለማስከበር የሚያስችለንን እርምጃ ሁሉ እንዲወስድ ታዟል**

«ውሳኔውን ፍትሐዊ አይደለም፣ ቀደም ሲል ቃል ስለገባን ብቻ ውሳኔውን እንቀበለዋለን» ከማለት አልተቆጠቡም:: ኢሳያስ የአረብኛ ቋንቋ ምሁርነታቸውና ስለ አረቦች ያላቸውን ግንዛቤ፣ በአረቦች መካከል ያለውን የእርስ በርስ ቅራኔ በማቀናጀት ለራሳቸው ጥቅም ሊያውሉት ይጥራሉ:: በባሕረ ሰላጤ ሁለተኛው ጦርነት ወቅት ከአንዱ ጋር በመወገን በሌላ ሀገር ላይ የውክልና ጦርነት አካሒደዋል:: በአሁኑ ወቅት ደግሞ ያን ግንኙነት በአፍጢሙ እንዲደፋ አድርገውታል::

አንዳንድ አረብ ሀገራት በመካከላቸው የሚፈጠረውን አለመግባባት ለመፍታት አረብ ባልሆኑ እንደ ኤርትራና ቱርክ የመሳሰሉ ሀገራትን ዕርዳታ ይሻሉ:: ይህ በእጅጉ አሳዛኝ ድርጊት ነው:: በአሁኑ ወቅት ሁሉም አረቦች የኢሳያስን መሰሪ ድርጊት የተገነዘቡ ይመስላል:: በየመን የእርስ በርስ ጦርነት በተካሔደበት ወቅት ኢሳያስ ከሁለቱም ተፋላሚ ወገኖች ጋር ስምምነት ከተፈራረሙ በኋላ ለአንዱ ወገን መሣሪያ ያቀብሉ እንደነበር ታውቋል:: ዛሬ ደግሞ በሱዳን ተመሳሳይ ሚና እያራመዱ መሆናቸው ያደባባይ ምስጢር ነው:: የሱዳንን ሉዓላዊነት፣ የግዛት አንድነት፣ ሰላምና መረጋጋት በኢሳያስ ጣልቃ ገብነት ምክንያት ለአደጋ መጋለጣቸው ከማናቸውም ታዛቢ የተሰወረ አይደለም::

እፎይታ:- የኤርትራ፣ የየመንና የሱዳን መቀራረብ በአፍሪካ ቀንድ ላይ የሚያሳድረው ተጽእና ደናር ይሆን?

ፕሬዚዳንት ጉሌድ:- እኛ ጥቅም ለሚያስገኝ መቀራረብና ግንኙነት እጃችንን እንዘረጋለን:: መልካም ግንኙነት ለአካባቢው ሕዝቦች ፋይዳ ያለው ነውና:: በዚህ ረገድ ከአካባቢውም ሆነ ሩቅ ካሉት ወገኖች ጋር መቀራረብና አብሮ መስራት መልካም ነው:: ይሁን እንጂ ኢሳያስ ከየመንና ከሱዳን ጋር ለመቀራረብ የፈለጉት ከኢትዮጵያ ጋር በገጠሙት ፍጥጫ ምክንያት ብቻ ነው:: ይህ ደግሞ ማናቸውም ታዛቢ ሊያረጋግጠው የሚችለው ሐቅ ነው:: ኢሳያስ አፈወርቂ በየትኛውም አቅጣጫ የሚገነቡት ግንኙነት ምንጊዜም የተወሰነ ግብ ያለው ነው:: ይኸውም ከተጋረጠባቸው መገለልና አጣብቂኝ የሚወጡበትን ስልት ለማመቻቸት ነው:: እንደሚታወቀው ሁሉ ኤርትራ በአሁኑ ወቅት ከኢትዮጵያ ጋር በፈጠረችው ፍጥጫ ምክንያት እውነተኛ የኢኮኖሚ ውድቀት አጋጥሟታል:: ኢሳያስ ምንም ያህል የገዘፈ ጥረት ቢያደርጉም ከዓረቦች አዕምሮ ሊፍቁት ከቶ የማይቻላቸው አንድ በዓረቦች ልቡና ላይ የተከተበና የተነቀሰ ጥቁር ትዝታ አለ:: ሐኒሽን በኃይል መውረራቸውን፣ የሱዳንን መንግስት ኤምባሲ አሳልፈው ለሱዳን መንግስት ተቃዋሚዎች መስጠታቸውን፣ በሱዳን ሕዝብ ላይ ጦርነት ማወጃቸውን ዓረቦች የሚረሷቸው አቋሞች አይደሉም::

ከኢሳያስ ጋር ግንኙነት መመስረት ያለበት ማናቸውም ወገን በቅድሚያ ትርፍና ኪሳራውን በሚገባ ማስላት ያለበት ይመስለኛል::

ጂቡቲ ከየመንና ከሱዳን ጋር ያላት ግንኙነት ሁለቱ ሀገሮች ከኤርትራ ጋር በሚኖራቸው አዲስ መቀራረብ ምክንያት ይጐዳል የሚል ግምት የለኝም::

እፎይታ:- የሶማሊያን ችግር ለመፍታት በየጊዜው ስለሚደረጉት ጉባኤዎች ምን

ስስተያየት ስለዎት?

ፕሬዚዳንት ጉሌድ:- አንድ እውነት አለ:: ሶማሌዎች የማይካፈሉበት ማናቸውም ጉባኤ ውጤታማ ይሆናል የሚል ግምት የለኝም:: የሶማሌን ችግር በሞግዚት አማካይነት ለመፍታት የሚደረግን ጥረት እንቃወማለን፤ የሽምጋዮች ሚና ሶማሌዎች ራሳቸው ችግራቸውን ለመፍታት የሚያስችላቸውን አመቺ ሁኔታና መስክ በመፍጠር ላይ ብቻ የተገደበ እንዲሆን እንጠይቃለን:: ከጦር አበጋዞችም ጋር ቢሆን ከቁጥብ መስተንግዶ ያለፈ ግንኙነት ሊኖር አይገባም:: እነሱ የሶማሊያን ሕዝብ የሚወክሉ አይደሉምና:: እነሱ ውሱን ቡድናዊ ጥቅም አስጠባቂዎች ናቸው:: ስለሆነም ጂቡቲ ከመሰረት ጀምሮ እስከ ጣራ ድረስ ያለውን የሶማሊያን ግንኙነት የመለወጥ አስፈላጊነት አጥብቃ ትጠይቃለች:: የሰላም ጥረቱ ሒደት በራሷ በሶማሊያ ውስጥ መጀመር አለበት:: ሁሉንም ተፋላሚ አንጃዎችንና ሁሉንም የሕብረተሰብ ክፍሎችን በአካተተ መልኩ ሶማሊያዊ መሰረት ያለው ሰላም መምጣት አለበት::

ዓለም አቀፉ ጉባኤ የሶማሊያን ችግር ለዓለም ሕዝብ በማስታወስ ረገድ ከፍተኛ ጠቀሜታ እንዳለው አይካድም:: የዓለም ማሕበረሰብ በአሁኑ ወቅት ለሶማሊያ ችግር አፅንኦት የሰጠው አይመስልም:: የአረብ ሀገራትም ቢሆኑ አለመታደል ሆኖ ለሶማሊያ ያለባቸውን ሐላፊነት በሚገባ አልተወጡም::

**እፎይታ:-** አንዳንድ የሶማልያ አንጃዎች ዕርዳታ እንዳናገኝ ኢጋድ ዕንቅፋት ሆነብን ይላሉ:: ምን ያህል እውነት ነው?

ፕሬዚዳንት ጉሌድ:- ይህ ትክክለኛ ያልሆነ ውንጀላ ነው:: ዕርዳታ አቅራቢዎች በሶማሊያ በተለይም በደቡቡ ክፍል የፀጥታው ሁኔታ አስተማማኝ ባለመሆኑ የተነሣ ዕርዳታ የማደሉን እንቅስቃሴ ለመግታት ተገደዱ:: ለዚህም ተጠያቂ የሚሆኑት ራሳቸው የአንጃ መሪዎቹ ናቸው:: የዓለም አቀፍ ድርጅቶች ወኪሎችን ያፍናሉ:: እነዚህ ሰዎች በዚያ የሚገኙት ለሶማሊያ ሕዝብ አስቸኳይ ዕርዳታ ለማድረስ ነው:: ኢጋድ በበኩሉ የሶማሊያ ሕዝብን መከራና ሰቆቃ ለማቅለል የሚችል ዕርዳታ ለማስገኘት ከፍተኛ ጥረት ያደርጋል:: ይህን መሰሉን ውንጀላ የሚያሰሙ ወገኖች በሶማልያ ሕዝብ ላይ የሚፈጽሙትን ወንጀል ለመሸፋፈን የዘየዱት ተንኮል ነው::

እኔ ሱማሌ እንደመሆኔ መጠን ይህ መሰሉ ሤራ ከየትኛውም አቅጣጫ ቢሆን ይከሰት ዘንድ አልፈቅድም:: በአሁኑ ወቅት እጅግ አሳዛኝ ሆኖ የተገኘው የሶማሊያ አንጃ መሪዎች በሶማሊያ ሕዝብ ላይ የጠነሰሱት ሴራ ነው::

**እፎይታ:-** ሶማሊላንድን በተመለከተ የጂቡቲ አቋም ምንድን ነው?

ፕሬዚዳንት ጉሌድ:- የሲያድ ባሬ መንግሥት ከወደቀ ማግስት ጀምሮ የሶማሊላንድን ጉዳይ ለጊዜው እናቆየው ብዬ ነበር:: ምክንያቱም ሶማሊላንድ ሰላምና መረጋጋት የሰፈነባት ስለሆነች አጣዳፊ የቤት ሥራ የምትጠይቅ አይደለችም:: ከሁሉ በፊት ሥርዓት አልበኝነት በተጠናወታቸው አካባቢዎች እንደ ሞቃዲሾና ደቡብ ሶማሊያ ባሉት አካባቢዎች መረጋጋት ማስፈን ይገባናል ብያለሁ:: በሀገሪቱ ማዕከላዊ ክልልም የሚካሔደውን ጦርነት ማስቆም ቅድሚያ ትኩረት የሚሰጠው አንኳር ተልዕኮ መሆን አለበት:: ከዚህ በኋላ የተዋሐደች ሶማሊያን መንግሥት የማዋቀሩን ሒደት ማጥናት በሚቻልበት ዘዴ ላይ ማሰብ ይቻላል:: ቀዳሚው ፕሮግራም በአነስተኛ ደረጃም ቢሆን እርስ በርስ የመተራረዱን ድርጊት ማስቆም ነው:: የተልዕኮው ፣ዓላማ በአነስተኛ ደረጃም ቢሆን ሶማሌዎቹ እርስ በርስ እንዲደማመጡ ማስቻል ቢሆን ይመረጣል:: ይህ ጉዳይ ሁነኛ ፈሩን ከመያዙ በፊት ስለመገንጠል ማውራት ጠቃሚ አይመስለኝም:: መላ ሶማሊያን ሥርዓተ አልበኝነት ባጥለቀለቀበት ሁኔታ ውስጥ ስለየትኛው የሶማሊያ ውሕደት ነው ማውራት የምንችለው?

ሶማሊላንድንና ሌላውን የሶማሊያ ክፍል በአንድ ዓይን ማየት አይገባንም:: ለሕዝቧ ሰላም፣ መረጋጋት፣ ክብርና ሞገስ ላጎናፀፈው ክፍል ተገቢውን ማበረታቻ በይፋ መግለፅ ይጠበቅብናል:: ስለሆነም በሶማሊላንድ ዙሪያ ያጠነጠነ ሙግት መቆም አለበት:: የሶማሊላንድን ተጨባጭ እውነታ እንቀበል ባይ ነኝ:: ሰብአዊ እርዳታ በማከፋፈል ሒደት ውስጥም ይህ ተጨባጭ እውነታ ከአእምሯችን ለአፍታ እንኳ ሊጠፋ አይገባም::

ይህም በበኩሉ በሶማሌዎች መካከል ወደፊት እንዲደረጉ ለምንመኛቸው ግንኙነቶች አመቺ ሁኔታ በመፍጠር ረገድ የሚኖረው እንደምታ ከፍተኛ ነው:: ይህ አሠራር የአረብ ሀገሮችም ሆኑ ሌሎች ከአንዱ ወገን ጋር በማበር ሌላውን የማግለል ፖሊሲ እንዳይከተሉ በማድረግ ረገድ ሁነኛ አስተዋጽኦ ይኖረዋል:: እኛ ለማናቸውም ቢሆን ዕውቅና አንሰጥም:: ወደፊትም ቢሆን ከዚህ የተለየ አቋም አይኖረንም:

**እፎይታ:-** የጂቡቲና የአረብ ሀገራት ግንኙነት ባሕርይን እንዴት ይገልጹታል?

ፕሬዚዳንት ጉሌድ:- እኛ ከአረቡ ዓለም አኳያ ያለን ግንኙነት ልዩ ነው:: እኛ ለአረቦች የተለየ ስሜት አለን:: በአረቦች ላይ ያሳደርነው ስሜት ግን ደካማ ይመስለኛል:: ከአረባዊም ሆነ ከአፍሪካዊ ሰብእናችን የሚመነጭ ሁነኛ አቋም ይዘን ሳለ በጂቡቲ አረባዊ አስተሳሰብ በእጅጉ የሳሳ ነው ማለት ይቻላል:: በሁሉም መስክ በጂቡቲ የባሕረ ሰላጤ አገራት ኢንቨስትመንት የለም:: ይህም ምናልባት የባሕረሰላጤውን ጦርነት ተከትሎ የመጣው ፖለቲካዊና ኢኮኖሚያዊ መመሰቃቀል የፈጠረው ሁኔታ ውጤት ሊሆን ይችላል:: በመላው የአረብ ዓለም የባሕረ ሰላጤ ሀገራት የጂቡቲን ኢኮኖሚ በመደገፍ ረገድ ቀዳሚ ሚና ይጫወቱ ነበር:: በአካባቢው በተከሰቱት ሁለት ጦርነቶች ምክንያት ሀገራቱ በውስጣዊ ጉዳዮቻቸው ዙሪያ ለመሽከርከር ተገደዋል:: ኢራቅ አሜሪካ የምትፈነጭባት መስክ ሆናለች:: አረቦች በአጠቃላይ በራሳቸው ላይ እየተጫወቱ ይገኛሉ:: በሊቢያ፣ በኢራቅና በሱዳን ላይ በተጣለው ማዕቀብ ላይ ትኩረት አይሰጡም:: በጦር መሣርያዎች ላይ ማዕቀብ የመጣሉ ጉዳይ እንዳለ ሆኖ በሕዝቦች ዕለታዊ ጉርስ ላይ የሚጣል ማዕቀብ መጣል ሕዝቦችን በረሀብ መቅጣት ተቀባይነት ሊኖረው አይገባም:: በሱዳን ላይ ድብደባ ማካሄድም ተቀባይነት የለውም:: በአንዲት ነፃ ሀገር ሉዓላዊነት ላይ የተፈፀመ ተቀባይነት የሌለው ድርጊት ነው:: ከዚህ አቋማችን በመነሳት የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ለዚህ የጠላትነት እርምጃ ተጠያቂውን ለይቶ እንዲያመለክት ጥያቄ አቅርበናል:: ሁለቱን የአሜሪካ ኤምባሲዎች ፍንዳታ ማን እንደፈፀመው ነጥሮ መውጣት አለበት:: አካላዊና ኢኮኖሚያዊ ጉዳት ለደረሰባቸው ወገኖች ካሳ እንዲከፈል

ዛሬም ከመጠየቅ አልቦዘንንም።

**እፎይታ፡-** አንዳንድ ወገኖች ጂቡቲ የኢትዮጵያ 15ኛ ክልል (Region) ሆናለች ሲሉ ተደምጠዋል። ስለዚህ ጉዳይ እርስዎ ምን ይላሉ?

**ፕሬዚዳንት ጉሌድ፡-** (ፈገግታ) እንዲህ ዓይነቱን አሉባልታ የሚነዙት የኤርትራው ፕሬዚዳንት ኢሳያስ አፈወርቂ ናቸው። ቀደም ሲልም በግልጽ ተናግረውታል። ሆኖም ይህ መሠረተ ቢስ ውንጀላ እምብዛም አያሳስበንም። ኢሳያስ ከዚህ ቀደም «አአድ የኢትዮጵያ ጭራ ነው፣ አረብ ሊግ የግብፅ ጭራ ነው፣ የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት የአሜሪካ ተቀጽላ ነው» በማለት ተናግረዋል። የኢሳያስ ውንጀላዎች ተከታታይነት አላቸው። ሆኖም ከኢትዮጵያ ጋር ባለን ግንኙነት ላይ አንዳችም ለውጥ ሊያመጡ አይችሉም። እነዚህ ውንጀላዎች ሐላፊነት የጎደላቸው በመሆናቸው ትኩረት አንሰጣቸውም።

**እፎይታ፡-** በታላላቅ ሃይቆች ሀገሮች አካባቢ ያለውን ሁኔታ እንዴት ይመለከቱታል?

**ፕሬዚዳንት ጉሌድ፡-** በዚያ አካባቢ አንድ ስሙን ልጠራው የማልሻው ጀብደኛ ሰው አለ። ይህ ሰው የአፍሪካን ቀንድ ከሚያውኩት ኢሳያስ አፈወርቂ ጋር አዲሱን ትውልድ ለመምራት የተቀቡ መሪዎች እንደሆኑ ምናባዊ ግምት ያሏቸው ናቸው። እነዚህ ሰዎች በሁለቱ አካባቢዎች ሽብር፣ ግድያና ውድመት እየዘሩ አካባቢውን ለውድቀት የዳረጉ ናቸው።

**እፎይታ፡-** በአባላቱ መናቆር የታወከው ኢጋድ ወደፊት እንደአንድ ድርጅት ለመቀጠል ያለው ዋስትና ምንድነው?

**ፕሬዚዳንት ጉሌድ፡-** አልደብቃችሁም። በዚህ አካባቢ ሕዝቦች መካከል ብቻ ሳይሆን በመሪዎቻቸውም መካከል ቢሆን ልዩነት አለ። ልዩነቱን በማባባስ ረገድ ኢሳያስ ትልቁን ድርሻ ይዘዋል። ከኢትዮጵያ፣ ከሱዳን፣ ከጂቡቲ፣ ከኬንያና ከኡጋንዳ ጋር ችግር ፈጥረዋል። ሰውየው ኢጋድን የራሳቸው የፍልሚያ መድረክ ለማድረግ ይሻሉ። ያም ሆኖ በኢጋድ የሚታየው ሁኔታ ከሌላው ሶስተኛ ዓለም በተለይም በአፍሪካ ውስጥ ከሚታዩት ልዩነቶች የተለየ አይደለም። ድንገት ደራሽ ችግር ነው። በአካባቢው ሕዝቦች መካከል ባለው ትብብር ላይ ደንቃራ ለመሆን የሚበቃ አይደለም።

**እፎይታ፡-** ፈረንሳይን በአሜሪካ የመለወጥ አዝማሚያ አላችሁን?

**ፕሬዚዳንት ጉሌድ፡-** ከፈረንሳይና ከአሜሪካ ጋር ያለንን ግንኙነት በተመለከተ ከመገናኛ ብዙሐን ብዙ እንሰማለን። ጂቡቲ ፕሮጀክት አለያም ከአንዱ ባለይዞታነት ወደሌላው የምትተላለፍ ሸቀጥ አይደለችም።

በዚህ ረገድ ቋሚ መርሕ አለን። ከፈረንሳይ ጋር ያለን ግንኙነት ስትራቴጂያዊና ወደ ኋላ ማፈግፈግን የማይፈቅድ ነው። በሌላ በኩል ደግሞ ለአሜሪካ የጦር ሠፈር ስለመፍቀድ ጉዳይ ሌላው ቀርቶ በሐሳብ ደረጃ እንኳ የለም። በዚህ ዙሪያ የተካሔደ ንግግርም የለም።

> ሚያዝያ 96 ላይ ኤርትራ በባብ.ኤልመንደብ ትይዩ በምትገኘው ዱሜራ በተሰኘችው የጂቡቲ አካባቢ ላይ አደጋ ለመጣል ቃጥታለች። በጂቡቲ ላይ ተፅእኖ ለማሳደር በአሰመ መልኩ የኤርትራ መንግሥት ዱሜራን በኤርትራ ግዛት ውስጥ የሚያካትት ካርታ አሳትሟል

ይሁን እንጂ በእኛና በፈረንሣይ መካከል ያለውን ግንኙነት ለመናድ ይህ ዓይነቱን አሉባልታ የሚነዙ ወገኖች አልታጡም። እኛ ለአሜሪካም ሆነ ለሌሎች ሀገሮች የጦር ሠፈር አንሰጥም። የፈረንሣይ የጦር ሠፈር ከነፃነት በኋላ ጀምሮ የነበረና ያለ፣ የወረስነው ነው። በሁለቱ ሀገሮቻችን መልካም ፈቃድና ስምምነት መሰረት የተመሠረተ ነው። ባለፉት ሁለት አሥርት ዓመታት ፈረንሣይ ጂቡቲን አስከፍታ አታውቅም። ወይም በጦር ሰፈሩ አላግባብ ተጠቅማለች የሚያሰኝ ሁኔታ እስከ ዛሬ ድረስ አልተከሰተም። ጦር ሠፈሮቹ ለእኛ ጥቅም የቆሙ እንጂ በኛ ላይ የቆሙ አይደሉም። የፈረንሣይ ዲፕሎማሲ ሚዛናዊና የሰከነ ነው። የጅቡቲያውያንን ስሜትና ባሕርይ በሚገባ ያገናዘበ ነው።

ከአሜሪካ ጋር ያለን ግንኙነትም መልካም ነው። ባለፉት ዓመታትም እድገት አሳይቷል። ይሁን እንጂ ከፈረንሳይ ጋር ካለን ጥብቅ ግንኙነት አኳያ የሚታሰብ አይደለም። እኛ ትንሽ ሀገር እንደመሆናችን መጠን እንደ አሜሪካ ካሉ ሀገራት ጋር ግንኙነት መፍጠር ትልቅ ፋይዳ እንዳለው እንገነዘባለን። የአሜሪካ አካባቢያዊና ዓለም አቀፋዊ ሚና የሚናቅ አይደለም። በአፍሪካ ቀንድ አካባቢ በሚታዩት ሁኔታዎች



ውስጥ የአሜሪካ ሚና የሚታወቅ ነው። የአፍሪካ ቀንድ የአሜሪካ መንግሥት አብይ የትኩረት አቅጣጫ መሆኑም የሚካድ አይደለም። ስለሆነም ከአሜሪካ ጋር የወዳጅነት ግንኙነት አለን።

**እፎይታ፡-** የቀይ ባሕር ደህንነት ጉዳይ በጂቡቲ ዕይታ ምን ይመስላል? ከቀይ ባሕር አዋሳኝ ሀገራት መዳኢ ደህንነት አኳያ የጂቡቲ ራዕይ እንዴት ይገለፃል?

**ፕሬዚዳንት ጉሌድ፡-** የቀይ ባሕር ደህንነት ከአካባቢውና ከዓለም አቀፍ ደህንነት ጋር በጽኑ የተቆራኘ ነው። ቀይ ባሕር በዓለም ላይ እጅግ ተፈላጊ ከሆኑ መተላለፍያዎች መካከል የሚመደብ ነው። ማንም ብቸኛ ባለይዞታ ሊሆንበት ከቶውንም የሚቻል አይደለም። ቀይ ባሕር ዓለም አቀፋዊ ባሕርይ ያለው እንደመሆኑ መጠን በዚያ አካባቢ የሚደረጉ እንቅስቃሴዎች

ለዓለም አቀፍ ሕጋዊነት የተገዙ መሆን አለባቸው:: የአዋሳኝ ሀገራት ድርሻ ደግሞ የዓለም አቀፍ ሕጋዊነትን ማክበር ነው::

ስለ ቀይ ባሕር ደህንነት ማውራት ከአካባቢው ሕዝቦች አቅም በላይ ነው:: ይህ አደገኛ እሳቤ ነው:: ቀይ ባሕር ክልላዊና ዓለም አቀፋዊ ጥቅሞች የሚገናኙበት መስመር ነው:: በተለይም የታላላቅ መንግሥታት ጥቅሞች የዓለም ታላላቅ መንግሥታት ማለትም አሜሪካ፣ ፈረንሣይና ብሪታንያ ማናቸውም የአካባቢው መንግሥታት ጥቅማቸውን ሊጐዳ የሚችል ሚና እንዲኖረው ፈጽሞ አይፈቅዱም:: ስለሆነም ፋይዳ በሌለው ጉዳይ ላይ እንኳ ስላንትያ ከመፍጠር እያንዳንዱ መንግሥት የራሱን የውኃ ድምበር አስከብሮ መኖር የቀይ ባሕርን ደህንነት ከማስከበር አኳያ ሁነኛ ዘዴ ነው::

**እፎይታ:-** **በአንዳንድ የአካባቢው መንግሥታት መካከል የተፈጠረው ውዝግብ በጅቡቲ ላይ የሚያመጣው እንድምታ ምንድነው?**

ፕሬዚዳንት ጉሌድ:- በአካባቢው መንግሥታት መካከል የሚፈጠር ማናቸውም ውዝግብ በጂቡቲ ላይ ብቻ ሳይሆን በአካባቢው ሀገራት ላይም አሉታዊ ተጽእኖ አለው:: በአፍሪካ ቀንድ አካባቢ የደረሱ አንዳንድ ችግሮችን እናስታውስ:: በመንግሥቱ ኃይለማርያምና በሲያድባሬ መካከል የተፈጠረውን ግጭት ተከትሎ የመጣው ሁኔታ የሶማሊያን መንኮታኮት አስከትሏል:: ስለሆነም በዚህ አካባቢ የሚደርሱ ግጭቶች ሁሉ ቀደም ሲል እንዳልኩት አሉታዊ ተፅእኖ አላቸው:: ከዚህ ሐቅ በመነሳት ጂቡቲ ከነፃነቷ ማግሥት ጀምሮ የምትከተለው መርሕ፣ በሌሎች ሀገሮች የውስጥ ጉዳይ ጣልቃ አለመግባት ነው::

**እፎይታ:-** **የፈረንሣይና የጂቡቲ ግንኙነት ከቅርብ ጊዜ ወዲህ እንደቀዘቀዘ ይወራል:: ምን ያህል እውነት ነው?**

ፕሬዚዳንት ጉሌድ:- በእኛና በፈረንሳይ መካከል ልዩነት አልተፈጠረም:: ከፈረንሳይ ጋር ያለን ግንኙነት ታሪካዊ፣ ጥልቅና ሥር የሰደደ ነው:: የጂቡቲን ሕዝብ ባህላዊ ይዘት የተመለከትን እንደሆነ ሥር የሰደደ ፈረንሳዊ ባህል ሆኖ እናገኘዋለን:: የጂቡቲ ብሔራዊ ቋንቋም ፈረንሳይኛ ነው:: ከፈረንሳይ ጋር ያለን ግንኙነት የ115 ዓመት ዕድሜ አስመዝግቧል:: እነዚህ ረዥም ዓመታት በጂቡቲያውያን ሁለንተናዊ ሕይወት ላይ ስሜት መፍጠራቸው አይካድም:: ፈረንሳይ በጂቡቲ ያላትን ኃይል የመቀነስ እርምጃ በራሷ በፈረንሳይ የሚወሰን እንጂ እኛ በቀጥታም ሆነ በተዘዋዋሪ እጃችንን የምንከትበት አይደለም:: ዕርዳታን በተመለከተ አንዳንድ መንግሥታት ለጂቡቲ የሚያቀርቡትን ዕርዳታ አቁመዋል:: በዚህ ረገድ ምስጉን ዕርዳታ የሚያቀርብልን ብቸኛ መንግሥት የፈረንሳይ መንግሥት ነው:: የጂቡቲ መንግሥትና ሕዝብ በዓለም ስለደረሰው የኢኮኖሚ ቀውስ ይገነዘባሉ:: ፈረንሳይ ለጂቡቲ የምታቀርበው ዕርዳታ መጠን መቀነሱ ከዚህ በላይ በተጠቀሰው ምክንያት መሆኑን መካድ አይቻልም:: የፈረንሳይን ዕርዳታ ከሌሎች መንግሥታት ጋር ማነጻጸር በእውነቱ ውለታቢስ የሚያሰኝ ይሆናል:: ሕብረተሰባችን የፈረንሳይ የዕርዳታ መጠን በመቀነሱ ምክንያት ጉዳት እንደደረሰበት መካድ አይገባም:: በጂቡቲ ወደብ የመርከቦችም እንቅስቃሴ መቀነስ የራሱ አሉታዊ እንድምታ አለው::

ቀደም ባሉት ዓመታት አንዳንድ የአረብ ባሕረ ሰላጤ ሀገራት ለጂቡቲ ዕርዳታ ይሰጡ ነበር:: አሁን ግን ከሳውዲ አረቢያ በቀር ሁሉም እጆቻቸውን ሰብስበዋል::

እኛ የአረብ መንግሥት እንደመሆናችን መጠን ከአረብ ሀገራት አኳያ በታሪካዊነቱ የሚታሰብ ጹኑ ግንኙነት አለን፤ ስለሆነም በአሁኑ አስቸጋሪ ወቅት አረቦች ጂቡቲን ችላ እንዳይሏት እንማፀናለን:: በዚህ አጋጣሚ በግልፅ ማስረዳት የምሻው አብይ ጉዳይ ከአራት ዓመታት ወዲህ ዕርዳታ ቢቋረጥባትም ጂቡቲ ዛሬም አለች:: ዕርዳታ አገኘችም አጣች የጂቡቲ ሕልውና ተጨባጭ እውነታ ነው::

**እፎይታ:-** **የኢጋድ የወቅቱ ሊቀመንበር እርስዎ ነዎት:: የሶማሊያን ችግር ለዘለቄታው ለማስወገድ ምን እየተደረገ ነው? ቀደም ሲል የነበሩትን አስታራቂ ሐሳቦች የመምከኑ ምክንያት ምን ይሆን?**

ፕሬዚዳንት ጉሌድ:- ቀደም ሲል የቀረቡት አስታራቂ ሐሳቦች ለሶማሊያ መንኮታኮት ምክንያት የሆኑ ጉዳዮችን በጥልቀት የመረመሩና ያገናዘቡ አልነበሩም:: ከሶደሬው ጉባኤ በስተቀር በዚህ ረገድ የሚቀርብ ሐሳብ ሁሉ ግልብና ከአንጀት ጠብ የሚል አልነበረም:: የሶደሬው ጉባኤ የሶማሌዎችን ችግር በሚገባ ያስታመመ ነበር ማለት ይቻላል:: ባለመታደል የሶማሊያ አንጃ መሪዎች እንደ ቀደምቱ ስምምነቶች ሁሉ የሶደሬንም ስምምነቶች አጨናገፉ:: ከዚህ በመለስ የቀረቡ ሐሳቦች ሁሉ ሶማሌዎችን ከመለያየትና የጦርነቱን ዕድሜ ከማራዘም በቀር አንዳችም ፖለቲካዊ ትሩፋት አላስመዘገቡም:: የጦር አበጋዞቹ ከአንዱ የዓረብ ሀገር ወደሌላው የዓረብ ሀገር የሚያደርጉት ዙረት የርስበርስ መተራረዱን ሒደት ይበልጥ አደፋፈረ::

ጂቡቲ ከሶማሊያ ጋር በብዙ መልኩ የምትዛመድ መሆኗ እየታወቀ፤ የአካባቢው ሀገሮች በሶማሊያ ጉዳይ ላይ ጂቡቲን አላማከሩም:: እኔ ሶማሌ እንደመሆኔ መጠን የሶማሊዎችን የልዩነት መስመር ጠንቅቄ አውቃለሁ:: የሶማሌዎች ችግር ለራሳቸው ለሶማሌዎች ቢለቀቅ መልካም ነው እላለሁ::

**እፎይታ:-** **የደቡብ ሱዳን ጉዳይ በቅርቡ መፍትሔ የሚያገኝ ይመስልዎታል?**

ፕሬዚዳንት ጉሌድ:- እኛ በኢጋድ እይታ ሁኔታውን ስንመለከተው ወደትክክለኛው አቅጣጫ እየተራመደ ያለ ይመስላል:: ሁለቱም ወገኖች የራስን ዕድል በራስ በመወሰን መርሕ ላይ ተቀራራቢ እይታ አላቸው:: ስለሆነም ከጠመንጃ ቋንቋ ይልቅ የውይይት ቋንቋን የመረጡ ይመስላል:: ሁለቱም ወገኖች ሰላማዊ አቅጣጫ የያዙ ይመስላል:: ችግሩ በመስጊድና በቤተ ክርስቲያን መካከል ከሆነ ጨርሶ መፍትሔ ሊኖረው አይችልም::

**እፎይታ:-** **ስራ መልቀቂያዎ ወቅት ደርሷልን?**

ፕሬዚዳንት ጉሌድ:- እኔ የሕዝቡን ስሜት በመጠባበቅ ላይ ነኝ:: የእኔ ከስልጣን መውረድ የሕዝቡ ፍላጐት ከሆነ ለመውረድ ዝግጁ ነኝ:: አልሐምዱሊላህ፣ የጂቢቲ ሕዝብ ሀገሩን መጠበቅ የሚያስችል አቅም በጨበጠበት ደረጃ ላይ አድርሼዋለሁ:: ዴሞክራሲያዊ ተቋማት ተደራጅተዋል:: እኔ በምታጣበት ጊዜ ሕገ መንግስታዊ ክፍተት አይፈጠርም:: ምክንያቱም የአንድነት መንፈስ በእያንዳንዱ ጂቡቲያዊ ሕሊና ውስጥ ሰርጿልና:: □

# ቅንጭብጭብ

«ፈረሴ ከምፅዋ ውሃ ሳይጠጣ ዘውድ ጭኜ ንጉስ ነገስት አልባልም»

*- ልጅ ኢያሱን ጠቅሶ «ጦቢያ» መፅሄት የውጊያውን መድረሻ ሲያመላክትና ሲቀሰቅስ*

***

«ግልፅ ሁን:: ግን ግልፅነትህ ገደብ ይኑረው:: ባልተማሩ ወገኖች (ሰዎች) መሀል ይበልጥ ግልፅ በሆንክ መጠን አጠገብህ ካሉት ጀምሮ (ሁሉም) በጭቃ እንደተከበበ ደረቅ መሬት እየረገጡህ ሊራመዱ ይፈልጋሉ::»

*- ሶቅራጥስ (ሪፑብሊክ ከሚለው ፅሁፍ)*

***

«እርዳታ ሁሉ የግድ በሬዲዮና በቴሌቪዥን መነገር የለበትም:: ... መረዳት ያለበት ወገን ካለ ይረዳል::»

*- አትሌት ኃይሌ ገ/ስላሴ ከፊልሙ የሚገኘውን ገቢ ከኤርትራ ለተፈናቀሉ ወገኖች ማቋቋሚያ እንዲውል ከመፍቀዱ አኳያ ሲናገር::*

***

«... እነሆ ከ50 ዓመት በኋላ ሁለተኛ የታሪክ አጋጣሚ ላይ እንገኛለን:: በዚህ ወቅት የኢትዮጵያ ህዝብና የኢትዮጵያ ሉአላዊነት ተደፍሮአል:: ዜጉች ለአገርና ለወገን ጥሪ ምላሽ እየሰጡ ነው::»

*- አቶ ክቡር ገና የአ.አ ንግድ ምክር ቤት 50ኛ ዓመት በአል ላይ ካሰሙት ንግግር::*

***

«ችሎታ የሚያንሰውንና እውቀት የሚጉድለውን ሰው የምታገኘው ሲያሳብቅ ብቻ ነው:: ሰብቅና አሉባልታ የማይምነት ብቸኛ መገለጫዎች ናቸው::»

*- ሄሮፋነስ (ከክርስቶስ ልደት በፊት 700 ዓመት የነበረ የግሪክ ፈላስፋ)*

***

'ጦርነቱን እስከ ቀይ ባህር ድረስ በመግፋት ኢትዮጵያ የቀድሞ ወደቦቿ ሙሉ ተጠቃሚ የምትሆንበት ጊዜው አሁን ነው' የሚሉ ወገኖች መብዛታቸው የታወቀ ሲሆን ከእነዚህም መካከል 'የአማራ ቡርዣዎች' ዋነኞዎቹ ናቸው::»

*- መብሩክ ጋዜጣ*

***

«በማናቸውም መንገድ ሁሉም ነገር መልካም ነው፤ አሁን እርሱም ፍርሀትን ማወቅ አለበት::»

*- ሼሊያ ካሲዲ የተባለች በቺሊ የምስጢር ፖሊሶች ተይዛ የተገረፈች እንግሊዛዊት ዶክተር፤ ስለቀድሞው የቺሊ ፕሬዝዳንት ስለ አውጉስቶ ፒኖሼ በቁጥጥር ስር መዋል የተሰማትን ስትገልፅ::*

***

«የሰላም ሂደቱን በፍፁም አንተወውም፤ ወደ አመፃና ፍጥጫ አንመለስም::»

*- የፍልስጥኤም ፕሬዝዳንት ያሲር አራፋት ከእስራኤሉ ጠቅላይ ሚኒስትር ቤንጃሚን ናትናያሁ ጋር የሽግግር የሰላም ስምምነት ከተፈራረሙ በኋላ ከተናገሩት::*

***

«... ስድሳ ሁለት ዓመት ወደ ሁዋላ መለስ ብለን እንድናስታውስ የሚያደርገን ጉዳይ ገጥሞናል - ወረራ:: እርግጥ ነው ያና ይሄ የሚያለያያቸው ነገር ይኖር ይሆናል:: የዘር ፍሬው ግን ያው ነው - ወረራ»

*- ማሀቶት ጋዜጣ*

***

«... ከአሁን በሁዋላ ከአቶ ኢሳያስና ከመንግስታቸው የሰላም መንገድ ይመጣል ተብሎ የሚታሰብ አይደለም:: ሰላም የማምጣት አቅምም ፍላጐትም የላቸውም:: የመኖር እድሜያቸውም እንደ መንግስቱ ሊታይ ይገባዋል:: አቶ ኢሳያስ ማድረግ የሚችሉትና ለማድረግም እየሞከሩ ያሉት አጥፍቶ መጥፋትን ብቻ ነው...»

*- አብዮታዊ ዴሞክራሲ ጋዜጣ*

***

«ኢሳያስ መለስን ካላነጋገርኩ ሲሉ አዳራሹን በጠበጡ»

*- ገመና ጋዜጣ የዋጋዱጉን ስብሰባ አስመልክቶ ያሰፈረው የዜና ርዕስ::*

***

«ኤርትራ ከኢትዮጵያ ጋር ተቀላቀለች እንደተባለ ስሞታና ሀሜታ እንዳይበዛ፤ ልባቸው እንዳይሸፍት ተባለና ይቺ ደሀ አገራችን ያፈራችው ሁሉ ወደ አስመራ እየተጫነ እዚያ ፈሰሰ»

*- ጦቢያ ጋዜጣ*

***

«የመላው አማራ ህዝብ ድርጅት ተቀዳሚ ም/ፕሬዚደንት ክቡር ቀኛዝማች ነቃጥበብ በቀለ ተቀማጭነታቸው በአዲስ አበባ የሆኑትን የአራት አገሮች ዲፕሎማቶችን ተቀብለው አነጋገሩ»

- አንድነት የመአህድ ልሳን

*- ዲፕሎማቶችን በማነጋገር የሚደርስባቸው ስለሌለ ፊታውራሪነት አይገባቸውምን?*

***

«የተለየ ነገር ለመስራት አንሻም፣ ግን ብዙ ነገሮችን በተሻለ እንሰራለን::»

*- የጀርመኑ ቻንስለር ገርሃርድ ሽሩደር ለህዝባቸው ከተናገሩት::*

***

«ኢሳያስ አፈወርቂ ሆን ብለው እኔን ለማናደድና ለባሰ የጤና መታወክ ለመዳረግ ሀሊናዬን በሚያደሙ ቃላት ሲወርፉኝ ነበር:: ሰውዬው የጤንነቴን ሁኔታ ይከታተላሉ:: የልብ ድካሜን በማባባስ ህይወቴን ለአደጋ በማጋለጥ ለፖለቲካ ፋይዳ የሚረዳ ቀውስ ጂቡቲ ውስጥ የመፍጠር አደገኛ የፖለቲካ ቁማር ይጫወቱ ነበር»

*- የጂቡቲው ፕሬዝዳንት ሀሰን ጉሌድ አፕቲዶን ስለ ኢሳያስ አፈወርቂ ከተናገሩት::*

***

«እኔም ሀገሬን መውደዴን የምደውልበት እንደሌለኝ ያውቃሉና ጌታዬን ለመውደዬ ዋጋ ወንድሜንና ልጆቼን የበላ የጉለሌ ምስጥ እንዲበላኝ ይፍቀዱልኝ»

*- ወልደማርያም አየለ በ1923 ከፃፉት ማስታወሻ የተወሰደ::*



ጃንጥላ















የሻዕቢያ መርሀግብር



የሻዕቢያ ጉዞ!

ወጣ ወጣና እንደሸምበቆ - ሻዕቢያ

የቱ ይሻላል? ጃንጥላ ወይስ ባርኔጣ

ወርሃ ኅዳር



# «በኅዳር አትበል ዳርዳር»

ከካህሳይ ገ/እግዚአብሄር

እነሆ ከሐምሌ ጀምረን ህዳር ላይ ደረስን፤ ስለወራቶች እየወጋን አምስት ወራት ተጓዝን፣ ተመስገን:: ህዳር አንድ ላይ ማደርን፣ መሰባሰብን ያመለክታል:: የጥጋብ፣ የእርካታ፣ የጨዋታ ወቅትም ነው ህዳር::

ባለፈው የእፎይታ እትም ስለ እሸቷ፣ አበባዋ ጥቅምት ስናወሳ በጥቅምት መወለድ የተደሰቱ እንስሳት ከየዘራቸው ጥቅምት በተወለደችበት ሰሞን የወለዱዋቸውን በገዐ በረከትነት ለአቶ ሐምሌና ወይዘሮ መስከረም ማስረከባቸውን አይተናል:: እንደታሰበው ሆነና እንስሳቱ ሁሉ ከጥቅምት ጋር አደጉ፤ ጥቅምትም ከቡችሎቹ ጋር እየፈነጠዘች፣ ከጥንዶቹ ጋር እየቦረቀች፣ ከበራሪዎች ጋር እየከነፈች፣ ከዘላዮች ጋር እየነጠረች፣ ከሯጮቹ ጋር እየፈነደቀች አደገች::

አቶ ሐምሌና ወይዘሮ መስከረም በኑሯቸው ደስተኞች ሆኑ፤ «ሁሉ በደጃቸው ሁሉ በቤታቸው» አይነት ባለፀጎች ለመሆን በቁ:: ብቻ እግዚአብሄርን አንድ ነገር ይለምኑት ነበር፤ ልጅ እንዲሰጣቸው፣ ወንድ ልጅ:: ፈጣሪያቸውም አላሳፈራቸውም:: ወይዘሮ መስከረም ጥቅምትን በወለዱ በሰባት ዓመታቸው ወንድ ልጅ ከነቃጭሉ ዱብ አደረጉ፤ ህዳር አሉት:: ጥጋብ፣ እርካታ ለማለት::

ጥቅምት ስትወለድ በገዐ በረከትነት የመጡት እንስሳት (የመጀመሪያዎቹ ለማዳ እንስሳት) እያደጉ እየተራቡ ሄዱ:: ስለበዙም ሰብሳቢ፣ ተንከባካቢ፣ ጠባቂ አስፈለጋቸው:: ህዳር እረኛቸው እንዲሆን ተወሰነ:: አጅሬ ህዳር ወደ ወተት ዓለም ገባ:: የፍየሉ፣ የግመሉ፣ የላሙ፣ የበጉ ወተት በእጁ፣ በደጁ ሆነለት:: ሲሻው እያለበ ሲፈልግ እየጠባ ወተቱን ይምገው ጀመር:: ቀስ በቀስም የእናቱ ፍትፍት፣ የከብቶቹ ወተት፣ የእናቱ ዳቦና ቂጣ፣ የማሽላና የገብስ ጥብስ እየጣመው መጣ:: እየዋለ ሲያድር ደግሞ የገዛ ቤቱም ያስጠላው ጀመር:: ውሎውን ብቻ ሳይሆን አዳሩንም ከብቶቹ ጋር አደረገ:: የተዋጣለት እረኛ ወጣው::

ዛሬም ድረስ ህዳር የእረኛው ወር ነው የሚባለው ከዚሁ ጋር በተያያዘ መልኩ ነው:: አለቃ ኪዳነወልድ ክፍሌ ባዘጋጁት መዝገበ ቃላት ህዳር ለሚለው ቃል በሰጡት ፍቺ ውስጥ «... እረኞች ውጭ የሚያድሩበት ወር» ይሉታል::

## እረኛና ህዳር

በሀገራችን «በህዳር አትበል ደርዳር» የሚል አባባል አለ:: እንደልብህ ብላ፣ አትግደርደር፣ ጊዜው የበረከት፣ የጥጋብ ጊዜ ነውና ለማለት ነው:: ከሁሉም በላይ ወርሀ ህዳር ለእረኞች የተመቸ ወቅት ነው:: እረኛ እንደ ዱር እንስሳት፣ እንደ ከብቱ፣ እንደ አእዋፋ ጠግቦና ረክቶ የሚውልበትና የሚያድርበት ወቅት ነው:: የሽንብራና የስንዴ እንኩቶ እያነኮተ የማሽላና የገብስ እሸት እየጠበሰ ራሱን የሚያዝናናበት በውርጭ ተኮራምቶና ተጨማዶ የከረመ ገላውን ፈታ፣ ፈካ የሚያደርግበት ወቅት ነው::

ነገሩን በተጨባጭ ለማየት እንችል ዘንድ ህዳር ወር የሚከናወኑትን ጥቂቶችን ተግባራት እንመልከት፤ ገበሬው በአብዛኛው የገብስ አጨዳና የባቄላ ሰበራ ስራውን የሚያከናውነው በህዳር ወር ውስጥ ነው:: እረኞች ከወፍ እኩል በማለዳ ተነስተው ከብቶቻቸውን አዲስ በታጨደው የቃርሚያ ማሳ ያሰማራሉ:: ከብቶቹ በየእህሉ መሀል ተደብቆ የከረመውን ለምለም ሳር ሲነጩ፣ እረኞች እሸት ፍለጋ ይሰማራሉ:: ወደ ስንዴ ነዶ ከምርም ያነጣጥራሉ::

እረኞች ነዶውን መዘው ሰው እያያቸው ይዘው አይሄዱም:: ነዶውን ከክምሩ ከመዥረጡ በኋላ እግሮቻቸው ላይ ያስሩታል:: ሲራመዱ ከአንድ ዛፍ ወይም ሐረግ ጋር ተጠላልፎ እንዳይጠልፋቸውም የዱላ ምርኩዛቸውን እየተመረኮዙ የክረምት ጉርፍ በቀደዳቸው ቦዮች እየተሹለኮለኩ ይሄዳሉ:: ትንሽ ራቅ እንዳሉ ያመጡትን የስንዴ ነዶ አንድ ላይ ሰባስበው ከቀበሮ ጉድጓድ ይከቱታል:: እንዳይታወቅባቸውም

ጉድጓዱን በእሾህ ይከድኑታል። ከዚያ በኋላ ጠዋት ጠዋት «ህዳርን የሚያጥኑ» በመምሰል እንኩቶአቸውን ያነኩታሉ። ለአረኛ የጥቅምትና የህዳር ብርድ መከላከያ መሳሪያዎቹ የእሸት እንኩቶና ጥብስ ናቸው።

እንኩቶና ጥብስ በሁሉም አካባቢዎች የሚዘወተሩ ቢሆንም በደበልጥ እንኩቶ በደጋ፣ ጥብስ በቆላ ይዘወተራሉ። በተለይ የማሽላ እሸት ማርና ወተትን ያስንቃል። በወርሃ ህዳር እረኛ ከአእዋፍ አፍ ጠብቆ ለፍሬ ከደረሰው የማሽላ እሸት መቅመስ ሲጀምር ወዘናው ሀሉ ይለወጣል። ፊቱ ይወዛል፣ ይበራል፣ ደረቱ ይሰፋል። ድምፁ ሳይቀር ይቀየራል፣ በአጠቃላይ መላአካላቱ ያሸታል። በገጠሪቱ ኢትዮጵያ ኮበሌና ኮረዳ ንብና አበባ የሚሆኑበት ጊዜ ቢኖር የህዳር ወር ነው።

በምስራቅና ምዕራብ ሐረርጌ ወጣቶች «ሽጉዬ» (የአካባቢው የባህል ጭፈራ) እየጨፈሩና እየተዝናኑ ውለው በየማሽላው እሸት ማሳ የሚያድሩበት ጊዜ ይዘው የአብሮ አዳር ወር ነው። በትግራይና ጉንደር ቆላማ አካባቢዎችም እረኞች ከብቶቻቸውን ይዘው ውጭ የሚያድሩበት፣ ቀን ቀን በየአውድማው ዙሪያ በተከመረው ገለባ ላይ ትግል እየገጠሙ «የእሸት ጡንቻቸውን» የሚፈትሹበት ጊዜ በህዳር ወር ውስጥ ነው የሚጀምረው።

የሰሜን ሸዋ ኦሮሞና አማራ እረኞች በወርሀ ህዳር የሚፈፅሙት ተግባር ግን ከሁሉ የበለጠ ነው። ማሽላው ሲሸት እረኛው ዓመታዊ የድግስ ዝግጅቱን ለማሰናዳት ሽር ጉድ ይላል። እረኛ ሁሉ እሸት ማሽላ ከጥንቅሽ አገዳው ጋር እየቆረጠ ያመጣል። ከመሀላቸው አንዱ ማሰሮ ከቤቱ «ሰርቆ» ያመጣል። ከፊሉ (እንደሚችለው) ደግሞ ሽንኩርት፣ ድምብላል፣ በሶቢላ፣ ቃሪያ የመሳሰሉትን ያቀርባል። የመጣው ቅመም በድንጋይ ከተፈጨና ማሽላው ከተንቀረቀበ (ፍሬው ከተለየ) በኋላ አንድ ላይ ከማሰሮው ውስጥ ይጨመራል።

በመቀጠል እረኛ ያመጣውን ጥንቅሽ እየጠመዘዘ (እየጨመቀ) ማሰሮው ውስጥ ማጠራቀሙን ይያያዘዋል። የጥንቅሽ ጭማቂው እንደተጠራቀመ የማሰሮው አፍ በዋርካ ቅጠል ይወተፋል። በላዩ ላይም በኮባ ቅጠል ይታሰራል። በመጨረሻ ማሰሮው መሬት ውስጥ ይቀበራል። የተቀበረበት ቦታ እንዳይታወቅ ሌሎቹ እንዳያዩት ላዩ ላይ ጠፍጣፋ ድንጋይ ለምልክትነት ይቀመጥበታል።

ከሶስት ቀናት በኋላ በስራው የተሳተፉ እረኞች ባሉበት የግብዣው ስነ ስርዓት ይከናወናል። በቅድሚያ ማሰሮው ከተቀበረበት ቦታ ይወጣል። የተሸፈነበት ቅጠል ገለጥ ሲያደርጉት በቅመማ ቅመምና በጥንቅሽ ጭማቂ ያበጠው የማሽላ እሸት አተር አተር አክሎ ዓይኑን እያጉረጠረጠ ብቅ ይላል።

ከዛም የአብይ ዛፍ ቅጠል መሬት ላይ ይነጠፍና እሸቱ ይዘረገፋል። ወዲያው እረኛ ሁሉ እንደማንኪያ የሚያገለግለውን የማሽላ ደረቅ ቅርፊት እየያዘ መመገቡን ይያያዘዋል። እሸቱን በእጅ መንካት ግን ፈፅሞ አይፈቀድም። በዚህ መልክ የተዘጋጀው የማሽላ እሸት ተበልቶ አይጠገብም ነው የሚባለው።

እንግዲህ ህዳር የእረኛ ወር ለምን እንደተባለ የገባችሁ ይመስለኛል። ህዳር ሲነሳ «የህዳር ሲታጠን» ጉዳይ መወሳቱ የግድ ነው። አዲስ አበባችንም በዓመት አንዴ ትታጠናለች። ህዳር 12ቀን በጢስ ትታፈናለች ብንለው ሳይሻል ይቀራል? ግን ለምን ህዳር ይታጠናል? በዚህ ጉዳይ ብዙ ተብሏል። በተለይ በአዲስ አበባ ህዳር 12ቀን የሚደረገው «ማዕጠንት» ሰዎች በድሮ ጊዜ በአዲስ አበባ ከተማ ተከስቶ ከነበረው የህዳር በሽታ ጋር ያያይዙታል። በወቅቱ በርካታ ሰዎችን የጨረሰውና ቀባሪ እስከማጣት ድረስ የነበረው ክፉ በሽታ የህዳርን ጭስ ፈርቶ ይሸሽ ወይም በሌላ አሁንም ቢሆን ማዕጠንት መታጠኑ ጉዳት የለውም። በተለይ በቆሻሻ ማዕበል ለተዋጠችው አዲስ አበባ፣ በዓመት አንዴ ቀርቶ በየቀኑም ቢሆን መታጠን ሲያንሳት ነው።

«የህዳር ሲታጠን» ጉዳይ ከህዳር በሽታ በኋላ የመጣ ልማድ ነው ወይስ ከዚያም በፊት ነበር? የዚህ ፅሁፍ አቅራቢ የእድሜ ባለፀጎችንና ምሁራንን አናግሮ ለማወቅ እንደተቻለው ህዳር ሲታጠን ከህዳር በሽታ በፊትም ቢሆን በሀገራችን የነበረና የቆየ ባህል ነው።

በገጠሪቱ ኢትዮጵያ በክረምት የታረመው አረም በየማሳው ዳርና ዳር ነው የሚከመረው። ይህ የአረም ክምር በጥቅምት ወር ይደርቃል። የማለዳው ብርድና ውርጭ የሚያይለው ደግሞ በጥቅምትና በህዳር ወሮች ነው። ውርጩ ሰውን ብቻ ሳይሆን እህሉንም ይጉዳል። ገበሬው አንድም ለራሱ ሙቀት፣ ሁለትም አካባቢውን ለማሞቅ ማለዳ ተነስቶ በእሸት ማሳ ዙሪያ የተከመረውን አረም ያቀጣጥላል። ይህን የሚያደርገው ህዳር ተጀምሮ እስኪፈፀም ድረስ ባሉ 30 ቀናት በሙሉ ነው።

ሰው ሁሉ በየማሳው ዳርዳር እሳት ስለሚያቀጣጥል አካባቢው በሙሉ በጢስ ይታፈናል። ህዳር ይታጠናል። ማለዳ ማለዳ በሚከናወነው የማጠንት ስራ ገበሬውና እረኛው ከማሳው እሸት እየጠበሰ፣ እንኩቶ እያነኮተ ቁርስ ብጤም ይቀማምሳል።

የህዳር ታሪክ ብዙ ነው። ቅዱስ ያሬድ ወራትን፣ ሳምንታትን፣ እለታትን እየሸነሸነ ባስቀመጠው የድጓ ድርሰቱ የመጀመሪያዎቹ የህዳር ስምንት ቀኖች በወርሐ ፅጌ (የአበባ ጊዜ) ውስጥ ያካትታቸዋል። ከህዳር ስምንት በኋላ ያለውን ጊዜ ደግሞ ዘመን አስተምህሮ ይለዋል። የዝግጅት፣ የመሰናዶ፣ የማስተማር ጊዜ እንደማለት ነው።

በተረፈ በህዳር ውስጥ በርካታ ታሪካዊ ክስተቶችም ተፈፅመዋል እስቲ ጥቂቶችን ላስተዋውቃችሁና የዛሬውን ላብቃ።

በመጨረሻ አንድ የረሳሁዋትን ነገር ላክል። ህዳር ህዳር ከተባለበት ምክንያቶች አንዱ በግንቦትና ሰኔ በየማሳው ተበትኖ የከረመው ዘር ፍሬ አፍርቶ፣ ጐምርቶ፣ ታጭዶና ተከምሮ በየአውድማው የሚሰበሰብበትና ጐተራ የሚከተትበት ወር በመሆኑ ነው።

# ሻዕቢያ ከታሪክ




(ከመገኔ ሱምቡሉ)

በ1952 (የዘመን አቆጣጠሮቹ በሙሉ እ.አ.አ ናቸው) በተባበሩት መንግስታት ድርጅትና በእንግሊዝ ውሳኔ መሰረት ኤርትራ ከኢትዮጵያ ጋር በፌዴሬሽን እንድትቀላቀል ተደረገ:: ፌዴሬሽኑ ግን የሰመረ አልነበረም:: በ1962 በአፄ ሀይለስላሴ ባላባታዊና አሐዳዊ አገዛዝ የኤርትራ ፌዴራላዊ ግዛትነት ተሰርዞ በሀይል ከኢትዮጵያ ጋር እንድትዋሀድ ተደረገ:: ኤርትራ የኢትዮጵያ አሐዳዊ መንግስት 13ኛዋ ጠቅላይ ግዛት ሆነች:: ይህ ድፍረት የተመላበት ድርጊት ለሶስት ተከታታይ አስርት አመታት የቀጠለውን ጦርነት አቀጣጠለ:: ጦርነቱ በሁለቱ ወገኖች በኩል ከፍተኛ ውድመት አስከትሏል:: ይህ አሰቃቂ ጦርነት ያበቃው በ1991 ደርግ ሲደመሰስ ነው:: ከደርግ መደምሰስ በኋላ በኢትዮጵያ የሽግግር መንግሥት፣ በአፍሪካ አንድነት ድርጅትና በተባበሩት መንግስታት ድጋፍና ትብብር በ1993 በተደረገው ሕዝበ ውሳኔ ኤርትራ ነፃ ሀገር ሆነች::

በ1991 ለ30 ዓመታት የዘለቀው የኢትዮጵያና ኤርትራ ጦርነት አከተመ:: በ1993 የኤርትራን መንግስት በመፍጠሩ ረገድ የታዩት ሰላማዊና በመግባባት መንፈስ ላይ የተመረኮዙት ተግባራትና ግንኙነቶች ከልዕለሀያላኑ መንግስታት ፍጥጫና ፉክክር ማብቃት ጋር ተዳምሮ በኢትዮጵያና በኤርትራ መካከል ብቻ ሳይሆን በአጠቃላዩ በአፍሪቃ ቀንድ የሰላም፣ የዕድገት፣ የፖለቲካ መረጋጋትና መልካም ጉርብትናን መመስረት አዲስ ዘመን መመጣቱን ያበሰረ ክስተት ተደርጐ ተወስዶ ነበር:: ይሁን እንጂ ከእርስበርስ ጦርነት በአስከፊ ድቀት ለወጡት ሁለቱ አገሮችና ሕዝቦች የፈካው መልካም ዕድልና ብሩህ ተስፋ ሻዕቢያ በድንገትና ሳይጠበቅ በከፈተው የወረራ ጦርነት የኢትዮጵያን ግዛት በመያዙ ለምልሞ የነበረው የሕዝቦች የሰላም ተስፋ መልሶ ጨለመ:: ሻዕቢያ የኢትዮጵያን ሉዓላዊነት በመድፈር የኢትዮጵያ ግዛት የሆነውን መሬት በኃይል ወርሮ ከያዘ ወዲህ የሻዕቢያ መንግስትና ሰራዊት መሰረተቢስ በሆነ የበላይነት ስሜት በመወጠር፣ በተስፋፊነት ርዕዮተዓለም በመመራት፣ ጭካኔ የተሞላበት የሽብርና የጭካኔ ተግባር በመፈጸም፣ የኢትዮጵያውያንን ኑሮ በማናጋት፣ ከአገር በማባረር፣ ሴቶችን አስገድዶ በመድፈር፣ በማሰቃየት፣ በመግደል፣ በመሰወር፣ በማፈስና በምስጢራዊ ስፍራዎች በማጐር (ethnic cleansig ) ዘመቻውን ገፍቶበታል:: የመቀሌና የአዲግራት ከተሞች ያለርሕራሔ በሻዕቢያ አውሮፕላኖች በቦምብ ሲደበድቡ የአደጋው ሰለባዎችም ንጹሐን የሕብረተሰብ ክፍሎች ሆነዋል:: በዚህም ሳቢያ ከ180 በላይ የሚሆኑ ሰዎች በአብዛኛው ሕፃናት፣ አረጋውያንና ሴቶች ቆስለዋል፤ ተገድለዋልም:: በሻዕቢያ አረመኔያዊ ወረራ 200 ሺ ያህል ሰዎችም በጦርነቱ ከተጐዱት ስፍሪዎችና ከአጐራባች አካባቢዎች ከኑሯቸው ተፈናቅለዋል::

ከ25ሺ በላይ ኢትዮጵያውያንም ለብዙ ዘመናት ለፍተው ያፈሩትን ጥሪትና ንብረት ተዘርፈው፣ ተገርፈው፣ ተዋርደውና ግፍ ተፈጽሞባቸው በጠመንጃ አፈሙዝ እየተገደዱ ከኤርትራ እንዲወጡ ተደርገዋል:: በብዙ ሺ የሚቆጠሩ የባድመ፣ የሽራሮ፣ የአሊቴና፣ የቡሬና የዛላምበሳ ነዋሪዎችም ከቤታቸውና ከመኖሪያቸው ተሰድደው እስከፊ ሕይወት ለመምራት ተገድደዋል:: የሻዕቢያ ሀይሎች በየደረሱበት ትምህርት ቤቶችን፣ ጤና ጣቢያዎችን፣ የእህል መጋዘኖችን፣ ቤተክርስቲያናትን አፈራርሰዋል:: በሀይል ከያዙዋቸውም አካባቢዎች ከፍተኛ ግምት ያለው ንብረት ዘርፈዋል::

በመቀሌና አዲግራት ከተሞች ላይ በተፈፀመው የቦምብ ድብደባ የተሰማው የሕፃናትና የሴቶች ዋይታ በሻዕቢያ ፋሽስቶችና ጀሌዎቻቸው አካባቢ የላቀ ፍስሐን የሚያላብስ ጀብድ አድርጐ በመውሰዱ የብሔራዊ ኩራታቸው መገለጫ አድርገውታል:: በሲ-ኤን-ኤንና በቢቢሲ ቴሌቪዥኖች እንደየነው በአስቃቂው ድርጊት የፈነደቁ የሻዕቢያ አጫፋሪዎች ልክ እንደሒትለርና ሙሶሎኒ የፋሺስት አሽርጋጆች በአስመራና በሌሎችም አካባቢዎች እየተቃቀፉ ደስታቸውን ሲገልፁ ተመልክተናል:: የኤርትራ ሬዲዮ ስርጭትና ጋዜጦችም በጦርነት ወሬና «በድል አድራጊነት» ዜና የተሞሉ ነበሩ::

ይህ የፋሽዝም አስቀያሚ መልክ በአፍሪካ ምድርም እያንሰራራ መሆኑን ያሳያል:: መጀመሪያ በሩዋንዳ፣ አሁን ደግሞ በኤርትራ ተከስቷል:: ዓለም አቀፉ ሕብረተሰብም በሻዕቢያ የተወሰደውን አሰቃቂ እርምጃ ግራ በተጋባ መንፈስ ተመልክቶታል:: በ1936 ኢትዮጵያ በፋሺስት ኢጣልያ በተወረረችበት ወቅት በዘመኑ የነበረው የመንግስታቱ ማህበር ጆሮ ዳባ ልበስ ብሎ ነበር:: በእዚያም የተነሳ ኢትዮጵያ ከፍተኛ ጉዳት ደርሶባታል:: በኢትዮጵያና በኤርትራ መሀከል መጠነ ሰፊ የሆነ አውዳሚ ጦርነት ከመነሳቱ በፊት አስፈላጊውን፣ ወሳኝ፣ ወቅታዊና ውጤታማ እርምጃ መውሰድ የግድ አስፈላጊ ነው::

የአፍሪካ አንድነትና የተባበሩት መንግስታት ድርጅቶችም ይህንን የሁለቱን ድርጅቶች መሰረታዊ ድንጋጌና መርህ የጣሰ፣ ቻርተሮቻቸውንም ያፋለሰ፣ የአካባቢውንና የዓለምን ደህንነትና ፀጥታ የሚያናጋውን የሻዕቢያ የዕብሪት ወረራ አላወገዙም:: በሻዕቢያ መንግስት ላይ የኢኮኖሚ ማዕቀብ ለመጣል እንኳን አልሞከሩም:: እስከዛሬ ድረስ ይዞት ከቆየው የኢትዮጵያ ግዛትም ለቅቆ እንዲወጣ አላስገደዱም:: የፈረንሳይ መሪ የነበሩት ጀኔራል ቻርልስ ዴ. ጉል «ከራሱ ሕዝብና ሀብት በስተቀር በመከራ ጊዜ መንግስት ወዳጅ የለውም» ያሉት ፍፁም ትክክል ነበር:: ወደፊት የታሪክ ድርሳናት ይህንን አሰቃቂ ክስተትና የዘመኑን የአረመኔነት ድርጊት ይመዘግቡት ይሆናል::

ዓለም አቀፉ ሕብረተሰብ ሻዕቢያ በኢትዮጵያ ላይ በፈፀመው የሚዘገንን ወንጀል ሳቢያ ሻዕቢያን ለመቅጣት ወሳኝ እርምጃዎችን ካልወሰደ አካሄዱ የተባበሩት መንግስታት ቻርተርንና ብዙዎቹን መሰረታዊ የሰብአዊነት መርሆዎችን ዋጋ ያሳጣቸዋል::

የኢትዮጵያ መንግስት የኤርትራ ወራሪ ሀይል ከያዘው ግዛት ሌላ በተጨማሪ መሬት ለመያዝ ወደትግራይና ወደአፋር ክልሎች ያደረገውን ሙከራ ከማምከን በስተቀር ጦርነቱ ውስጥ ዘሎ አልገባም:: ይልቁንም የኤርትራ መንግስት በሀይል ከያዛቸው አካባቢዎች ለቅቆ እንዲወጣና ውዝግቡም በሰላማዊ መንገድ እንዲፈታ የኢትዮጵያ መንግስት በተደጋጋሚ ጠይቋል:: የጦርነት ሁኔታዎችን በወዳጅነትና በወንድማማችነት ምክክር ለመጨረስ የአካባቢ.ና የዓለም አቀፍ የሽምግልና መንገዶችን ሁሉ በመጠቀም ሰላማዊ መፍትሔም ለማምጣት ከፍተኛ ጥረት አድርጓል:: የሻዕቢያ አመራር ግን በኢትዮጵያ በኩል የቀረበለትን የሰላም ጥሪ በማጣጣልና የአፍሪካ አንድነት ድርጅትንና የተባበሩት መንግስታት የፀጥታው ምክር ቤት ያሳለፏቸውን ውሳኔዎች ባለመቀበል ከባድመ፣ አሊቴና፣ ሽራሮና ከሌሎችም አዋሳኝ አካባቢዎች ሀይሉን አላስወጣም::

የቀድሞው የተባበሩት መንግስታት ዋና ፀሐፊ ቡጥሮስ ቡጥሮስ ጋሊ በስልጣን ላይ በነበሩበት ጊዜ ለተባበሩት መንግስታት የፀጥታው ምክር ቤት ስለ «የዕቀባ ዲፕሎማሲ፣ ስለ ሰላማዊ እርቅና ስለ ፀጥታ ማስከበር» ደጋግመው የተናገሩትን እዚህ ላይ መጥቀሱ ተገቢ ይሆናል:: ግጭቶች በሚፈጠሩበት ወቅት ሰላማዊ መፍትሔ ማስገኛ ዕድሎች ተሟጥጠው ካለቁ የተባበሩት መንግስታት ዓለም አቀፍ ፀጥታን ለማስከበር የሚያደርገውን ጥረት አስተማማኝነት ለማረጋገጥ ወታደራዊ እርምጃ መውሰዱ አስፈላጊ ይሆናል ብለው ነበር ጋሊ:: በተመሳሳይ ሁኔታ ምንም እንኳ ከሻዕቢያ በኩል አንዳችም አዎንታዊ ምላሽ ያልተገኘ ቢሆንም ኢትዮጵያ እስከአሁን እንደምታደርገው በትዕግስት ግጭቱን በሰላማዊ መንገድ ለመፍታት የተያዙት ጥረቶች ከመከኑና ዕድሎቹም ተሟጥጠው ካለቁ ሉዓላዊነቷን ለማስከበር ኢትዮጵያ የሚኖራት አማራጭ ጦርነት ብቻ ይሆናል:: ጦርነት ሁላችንንም ወደጥፋትና ውድመት ይመራናል:: ቀጣዩ የኢትዮጵያና ኤርትራ ጦርነት አስከፊ ደም መፋሰስንና በሁለቱ አገሮች መካከል የማይሽር ቁስል ጥሎ እንደሚያልፍ ሁሉም ተገንዝቦታል:: ግን መሬታችን በወራሪዎች ተይዞ ሕዝባችን በየዕለቱ እየደማ ምን ማድረግ

«በኢህአዴግ ብርቱ ድጋፍ ኤርትራ በ1993 ነፃነቷን ተጐናፀፈች:: ሰባት ዓመት ባልሞላ ጊዜ ውስጥም የሻዕቢያ አመራር ያንን ሁሉ ትምህርት ረሳው»

እንችላለን? እርግጥ ትዕግስትም ገደብ አለው በማለት የኢትዮጵያ መንግስት በወቅቱ ተገቢውን ወታደራዊ እርምጃ አልወሰደም የሚል ስሞታ በሕዝቡ ዘንድ ይሰማል:: የኢትዮጵያ መንግስት የአገሪቱን ሉዓላዊነትና ብሔራዊ ፀጥታ ለማስከበር በወራሪው ሀይል ላይ ወታደራዊ እርምጃ መውሰዱ የማይቀር ነው:: የሰላሙ መንገድ ካላዋጣ ከባድ ዋጋ ተከፍሎ ወራሪውን ኃይል ማባረር የግድ ነው:: ለተባበሩት መንግስታትና ለአፍሪካ አንድነት ድርጅት በማመልከት ብቻ የአገራችንን ዘላቂ ሰላም ለማረጋገጥ አንችልም:: ኤርትራንና ሻዕቢያን በተባበሩት መንግስታት የፀጥታው ምክር ቤትም ሆነ በጠቅላላ ጉባኤው ላይ በመክሰስም ብሔራዊ ኩራታችንን ለማስጠበቅ አንችልም:: ስለዚህም ብሔራዊ ክብራችንን፣ ሰላማችንንና መሬታችንን ለማስመለስ ለጦርነት መዘጋጀትና ወታደራዊ እርምጃ መውሰዳችን አይቀርም:: «ሰላምን ከፈለግህ ለጦርነት ተዘጋጅ» እና «ጥሩ አጥር መልካም ጐረቤትን ይፈጥራል» እንዲሉ

# የማይማር ድርጅት

ማለት ነው:: የሰላሙ መንገድ ካላዋጣ ጦርነት አይቀሬ ሆኗል:: ውጤቱም ለኤርትራውያን ብሔራዊ ክብርን ወይም ብሔራዊ ውርደትን ያጐናፀፍ እንደሆነ ወደፊት የሚታይ ውጤት ይሆናል:: ወራሪዎች ሁልጊዜም በጦር ሜዳ የሚደመሰሱና የሚዋረዱ መሆኑን ታሪክ በተደጋጋሚ አረጋግጧል::

በ1891 ኢጣሊያ ኢትዮጵያን ለመውጋትና ቅኝ ግዛት ለማድረግ አስፈላጊውን ቅድመ ዝግጅት ሁሉ አጠናቅቃ ከፍተኛ ቁጥር ያለው ሰራዊትና ግዙፍ ዘመናዊ መሳሪያዎችን በምፅዋ ወደብ በኩል በምስጢር እያስገባች የመሆኗ ዜና በዳግማዊ ምኒልክ ይመራ በነበረው የኢትዮጵያ መንግሥት ዘንድ እንደተሰማ ዳግማዊ ምኒልክ ሚያዝያ 10 ቀን 1891 የኢትዮጵያን ብሔራዊ ድንበር በመግለፅ ኢጣሊያንን ጨምሮ ሁሉም የአውሮፓ አገሮች የኢትዮጵያን ሉዓላዊነት እንዲያከብሩ የሚጠይቅ ደብዳቤ ለአውሮፓውያን መንግስታት ሁሉ አሰራጩ:: የንጉሰ ነገስቱ መልዕክት ግልፅና ቁርጥ ያለ ነበር:: መልዕክቱም፣ «እነዚህ ድንበሮቻችን ናቸው:: እባካችሁ አክብሯቸው:: ድንበሮቻችንን ካልተከበሩ ግን እጃችንን አጣጥፈን አንቀመጥም:: ተስፋችንን በእግዚአብሔር አድርገን ወረራን እንቋቋማለን» ይላል::

ኢጣልያ ግን ግልፅና ቁርጥ ላለው ለንጉሰ ነገስት ምኒልክ መልዕክት ክብርና ሞገስ አልሰጠችውም:: ይልቁንም በዝግጅቶቹ ገፍቶ በትግራይ ክልል የሚገኘውን አድዋን ወረረች:: ምኒልክም ኢትዮጵያ የከፋ አደጋ ላይ መውደቋን በመገንዘብ ለኢትዮጵያውያን በመላ የክተት ጥሪ አድርገው የጦርነት ዝግጅታቸውን ያፋጥኑ ጀመር:: የአገሪቱ ታላላቅ የጦር አበጋዞችና ገበሬዎችም ለቀረበላቸው ብሔራዊ ጥሪ ፈጣን ምላሽ በመስጠት ከአራቱም ማዕዘናት ተሰባስበው ከፍተኛ ቁጥር ያለው ሰራዊት በመፍጠር ወደጦሩ ግንባር ወደአድዋ ተመሙ:: ከስፍራውም እንደደረሱ ኢትዮጵያውያኑ ፀንተውና ጠንክረው በመቆምና በጀግንነት በመዋጋት የጠላትን ሀይል አደቀቁት:: በመጋቢት 1/1896 21ሺ ዘመናዊ መሳሪያ የታጠቁና በአምስት ልምድ ባላቸው ጄኔራሎች የሚመሩ የኢጣልያን ወታደሮች 90 ሺ ኋላቀር መሳሪያ ጦርና ጉራዴ ከያዙ የኢትዮጵያ ተዋጊ ሰራዊት ጋር ተጋጥመው ከፍተኛ ጦርነት አካሔዱ:: ጦርነቱ ለ10 ሰዓታት ያህል ተካሔደ:: የኢጣልያን ሀይል በጦርነቱ ተደመሰሰ:: የኢትዮጵያ ድል አድራጊነትም ጦርነቱ በኢትዮጵያ ተደመደመ:: ጦርነቱ በጊዜው የነበረውን የነጮች ሀያል ተዋጊነትና አይበገሬነት ስሜት በማምከንም በዓለም ሁሉ አነጋገረ፣ ተደነቀም:: ድሉ የኢትዮጵያውያንን ጀግንነትና አገር ወዳድነት በማረጋገጥ በታሪክ ሰነዶች ተመዘገበ:: ዛሬ ከ102 ዓመት በኋላ በቡሬ፣ በባድመና ሽራሮ ተመሳሳይ ሁኔታ ተፈጥሮ ዓይናችን ስር ተደቅኗል:: ጦርነቱ ከተጀመረ ውጤቱ በ1896 በአድዋ ከተገኘው ድል የተለየ አይሆንም:: ጦርነቱ በሁለት እህትማማች ሀገር መሆኑ ግን ያሳዝነናል::

በጦርነቱ እንደምናሸንፍ እርግጠኞች የሆነው ለምንድነው? ግዙፍ የምጣኔ ሀብት ምንጭና ወደ60 ሚሊዮን የሚጠጋ ሕዝብ ያለን ትልቅ አገር ስለሆን ነው? ወይስ እያሌ ሰራዊትና በቂ ዘመናዊ የጦር መሳሪያ ስላለን ነው? በከፊል ሊሆን ይችላል:: ወሳኙ ምክንያት ግን እኛ የምናካሒደው ጦርነት ፍትሐዊና ሕጋዊ ስለሆነ ነው:: እኛ ወራሪዎች አይደለንም:: ጦረኛና አምባገነን በሆኑት የሻዕቢያ መሪ በኢሳያስ አፈወርቂና በአጫፋሪዎቻቸው የምትመራው ኤርትራ ናት:: ለሀገር ሉዓላዊነት ለማስከበር ትግሎች እንደሚመሰክሩት ማንኛውም አገር በወታደራዊ አቅሙ ጥንኳ /ሬሬው ኃያል ቢሆንም እንኳ በማንኛውም አገር ላይ የራሱን ፍላጐት መጫን ወይም በሀይል ኢኮኖሚያዊ ጥቅሞችን ማስከበር፣ የሌላውን አገር ሉዓላዊነት መድፈር የሌላ አገር ይዞታ የሆነውን መሬት መያዝና መቆጣጠር በፍፁም አይችልም::

ለምንድነው ይህ ትምህርት እስካሁን ያልተቀሰመው? ለምንድነው አሁንም አንዳንድ መሪዎች በሌሎች አገሮች ላይ ወታደራዊ የበላይነትን ለማረጋገጥ የሚፈልጉት? የሻዕቢያ መሪዎች ይህንን ሐቅ ለምን ይዘነጉታል? የአፄ ኃይለስላሴና የኰሎኔል መንግስቱ መንግስታት የኤርትራን የነፃነት ተጋድሎ ለመጨፍለቅ ያደረጉት ተከታታይ ጥረት ከፍተኛ እልቂትና ውድመት አድርሷል:: ትግሉ ድፍን 30 ዓመታት ወስዷል:: በመጨረሻም በኢሕአዴግ ብርቱ ድጋፍ ኤርትራ በ1993 ነፃነቷን ተጎናፀፈች:: ሰባት ዓመት ባልሞላ ጊዜ ውስጥም የሻዕቢያ አመራር ያንን ሁሉ ትምህርት ረሳው:: ከሁለት አስርት ዓመታት በፊት በዚያድ ባሬ የሚመሩ የሶማሊያ ሀይሎች ከሶቭየት ሕብረት ባገኙዋቸው ከፍተኛ ዘመናዊ መሳሪያዎችና በሰለጠኑ ወታደሮች በመተማመን የኢትዮጵያን ዳር ድንበር በመጣስ እስከድሬዳዋ የዘለቀ ወረራ ፈፀሙ:: የኢትዮጵያ ሉዓላዊነት በመደፈሩ የሕዝቡ ቁጣና እንደ እሳተ ጐሞራ ነው የፈነዳው:: በተላለፈው የክተት ጥሪ መሰረት ወንድ፣ ሴት፣ ወጣት፣ ሽማግሌ ሳይል ሕዝቡ ከዳር እስከዳር ተንቀሳቅሶ አገር ወዳድነቱን አስመሰከረ:: ብሔራዊ ክብሩን ለማስጠበቅ በመዝመት አንድ ወር ባልሞላ ጊዜ ውስጥ የሶማሊያን ወራሪ ሀይል ከኢትዮጵያ መሬት ጠራርጐ አስወጣ፣ ዳር ድንበሩንም አስከበረ:: ይህ ዕውነት በራቁትም ሆነ በቅርቦቹ ዓመታት የተረጋገጠ ነው:: ይህ ለማንኛውም ወራሪ ኃይል ትምህርት የሚሰጥ እብነት ነው::

እያሌ አስርት ዓመታት ፈረንሳይ፣ እንግሊዝ፣ ፖርቱጋል፣ ስፔይን፣ ቤልጂየምና ዩናይትድስቴትስ ኦቭ አሜሪካ «ስልጣኔን» የማዳረስ ተልዕኮ አለን በማለት ብዙ አገሮችና መንግስታትን በቁጥጥራቸው ስር ለማዋል ሞክረዋል:: ተልዕኮው ግን የቅኝ ግዛት ፖሊሲን በማራመድና ሕዝብን በባርነት የመግዛት፣ የማሰቃየት፣ በአጠቃላይ ግፍ የመፈጸም፣ ባንድ ቃልም አገሮቹን የመውረር ጦርነት ሆነ:: ውጤቱ ግን ወራሪዎችና ቅኝ ገዥዎች ተደጋጋሚ ሽንፈትና ውርደት እንዲጎነጩ አደረገ::

ከ1946 እስከ 1954 ፈረንሳይ፣ በቬይትናም ላይ ጦርነት ከፈተች:: ሆኖም ፈረንሳዮች ዘመናዊ የጦር መሳሪያዎች ታጠቁ ቢሆኑም በጦርነቱ ተሸናፊዎች ሆኑ:: ፈረንሳዊው ጦርመሪ ጄኔራል ናቫና የዲየንቢየንፉን ከተማን የማትደፈር ምሽጉ እንደሆነች ገለፀ:: ይህም ሀሳብ ከተማይቱን ጎብኝቶ ከነበረው አሜሪካዊ ጄኔራል ኦ. ዳንኤል ሀሳብ ጋር አንድ ነበር:: ነገር ግን ከ55 ቀናት በኋላ ቬይትናማውያን በከፈቱት የማጥቃት ዘመቻ የፈረንሳዮች ይዞታ እንዳልነበር ሆነ:: የኢፍትሐዊ ጦርነት መጨረሻ ምንጊዜም ቢሆን አሳፋሪ ሽንፈት ነው የሚሆነው::

ከአስርት ዓመታት በኋላ የአሜሪካ ሰራዊትም እንድን አገር መውረር ከፍተኛ ኪሳራ እንደሚያስከፍል ከማየቱም በላይ ቬይትናማውያን ለታላቅ ሽንፈት ዳርገውታል:: የአሜሪካ ሰራዊት በስምንቱ ዓመታት ጦርነት በመቶ ሺዎች የሚቆጠሩ ሰዎችን ሕይወት አጥቶ ተሸንፎ ቬይትናምን ለቅቆ ወጣ:: አሜሪካኖች ምንም እንኳን ሀያላን ቢሆኑም በጣም ትንሽ በሆነች አገርም ላይ ቢሆን የራስን ፍላጐትና ምኞት በሌላው ላይ ለመጫን መሞከር ከንቱ እንደሆነም ተረድተዋል:: እንኳንስ ትንሿ አገር ኤርትራ በትልቁ አገር ኢትዮጵያ ላይ ፍላጎቷን ልትጭን ቀርቶ ትልቋ ሀገር አሜሪካም በትንሿ ሀገር ቬይትናም ላይ ፍላጎቷን ለመጫን አልቻለችም::

የጦርነቱ እሳት ከመቀጣጠሉ በፊት ሻዕቢያ ካለፉት ሁኔታዎች ተምሮ ወራሪ ሀይሉን ከኢትዮጵያ መሬቶች ያስወጣል ወይስ በአሻፈረኝ ባይነቱ ገፍቶ የእሳት እራት ሆኖ ይቀራል? ጊዜ ውጤቱን ወለል አድርጎ ያሳየናል:: □



## የኢትዮጵያ ቴሌኮሙኒኬሽን ኮርፖሬሽን

## Ethiopian Telecommunications Corporation




☎ 510500 TLX 21000 ✉ 1047

ኢ-ሜይል etc-hq.@telecom. net. et.

ለተጨማሪ መረጃ

**Ethiopian Telecommunications Corporation**

# የተፈጥሮ ሙጫ ምርትና ገበያ ድርጅት

# NATURAL GUM PROCESSING & MARKETING ENTERPRISE

ድርጅታችን የተለያዩ ዓይነትና ደረጃ ያላቸውን የተፈጥሮ ሙጫ ምርቶች በማምረትና በማዘጋጀት ለውጭ ሀገርና ለሀገር ውስጥ ገበያ ያቀርባል::

### ምርቶቻችን

- ዕጣን (የተለያዩ ዓይነትና ደረጃ)
- ከርቤ (የተለያየ ደረጃ)
- ሙጫ (የተለያየ ዓይነት)
- አበከድ

ምርቶቻችን ለተለያዩ ማለትም ለምግብ፣ ለመጠጥ፣ ለመድኃኒት፣ ለሽቶ ለወረቀት ለቆዳ፣ ለጨርቃጨርቅ፣ ለመስታወት፣ ለጎማ፣ ለማዳበሪያና በአጠቃላይ ለ18 ዓይነት ኢንዱስትሪዎች በጥሬ ዕቃነትና ለቤት ውስጥ፣ ለቤተክርስቲያንና ለመስጊድ በጥሩ መዓዛው ለጭስነት እንደሚያገለግል ያውቃሉ?




**አድራሻ**

**Address**

✉ 62322 ☎ 159930/ 159932

Telex 21336

Telegram 11537

Fax 251-1-518110

Addis Ababa, Ethiopia

Our Enterprise by producing and processing different types and grades of Natural Gums. it supplies to the foreign & local market.

Our Products are

- Gum Olibanum (Various types & grades)
- Gum Myrrh (Various grades)
- Gum Arabic (Various types)
- Gum oppoponex

Our products are used as a raw material for various industries, which will reach about 18, such as for Food, Beverage, pharmaceuticals, cosmetics, paper, Leather, Textile, Glass, Rubber, Fertilizers, etc... & In churches, Mosques, and the Households to give a pleasant Odor when it burnt. Do You know this?

ይጎብኙን በምርቶቻችን ጥራትና በመስተንግዶዋችን ይረካሉ!

Come & Visit us! You will be satisfied by our product's quality & service.

# ጭንቀትና ተቋቁሞው



(ከህዲስ ሳህሌ)

ፍርሃት መንስኤው ምን እንደሆነና ምን ሊያስከትል እንደሚችል ስለምናውቅ እንሰጋለን:: ጭንቀት ግን መንስኤውንም ሆነ ተከታዩ ነገር ምን ሊሆን እንደሚችል አናውቅም:: ይህ አለማወቃችን ደግሞ «ምንድን ነው ነገሩ?» ያሰኘናል:: እናም ያስጨንቀናል:: ብዙ ጊዜ ምን እንደምንፈራ ልንናገር እንችላለን:: ምን እንደሚያስጨንቀን ግን አናውቀውም:: እንዲያው ዝም ብሎ ጭንቅ ጥብብ ይለናል:: እዚህ ላይ ግን ፍርሃትና ጭንቀት ተለያዩ ማለት አይደለም:: እንዲያውም ፍርሃት ሲበዛ ወደ ጭንቀት ይለወጣል:: የሥነ ልቡና ጠበብቱ እንደሚሉትማ የጭንቀት አንደኛው ምክንያት በስውሩ የአእምሮ ክፍላችን (Unconscious mind) ውስጥ የተጠራቀመው ፍርሃት ውጤት ነው::

በኑሮ ሂደት ውስጥ የተለያዩ ነገሮች ያጋጥሙናል:: ከእነዚህ ነገሮች ጋር በምናደርጋቸው ተራክቦ ወይም ግንኙነት ልምድ እያካበትን እንሄዳለን:: አዳዲስ ነገሮችም በገጠሙን ቁጥር እንደየሁኔታው ቀደም ሲል ያገኘናቸውን ልምዶች እየተጠቀምን እንቋቋማቸዋለን:: በዚያው ልክ ያካበትናቸው ልምዶች እማይበግሯቸው አዳዲስ ክስተቶች በየጊዜው ያጋጥሙናል:: በተለይም በጎ ገፅታ የሌላቸው ወይም የመሰሉን ክስተቶች ሲያጋጥሙን ማጣፊያው ያጥረናል:: እንደየሁኔታው እንፈራለን፣ እንጨነቃለን፣ ተስፋ ወደመቁረጥም እንደርሳለን:: ይሁን እንጂ ህይወት ነችና እጅ አንሰጥም:: በአልሞት ባይ ተጋዳይነት አውቀንም ይሁን ሳናውቅ እንፍጨረጨራለን:: የጎበጠውን እናቃናለን:: ዓልመን የሳትነውን በሌላ መንገድ ደግመን እንሞክረዋለን:: እናም ይሳካልናል፣ ያሰብነው ይደርስልናል::

ይሁን እንጂ አንዱ እንዳለው «ሕይወት ከደስታ ወደደስታ ሳትሆን ከፍላጐት ወደ ፍላጐት ነች::» ስለዚህ እንደገና ደሞ ለሌላ ታርጌት እንዘገጃጃለን:: ያሰቡትን ወዲያው ማግኘት ያልተለመደ ነውና አዲስ ጥረት ያስፈልገናል:: ይህ ደግሞ እንደገና ሊያስጨንቀን ይጀምራል:: ይህን ስናስብ «ጭንቀት አስፈላጊ ይሆን እንዴ?» ወደሚለው ጥያቄ እንሄዳለን::

ለጥያቄያችን መልስ ለመስጠት እሚሽቀዳደመው ብዙ ነው:: መልሱ ቀላል ነዋ! «እንዴታ! ጭንቀትማ ለሕይወት አስፈላጊ ነገር ነው::» እሚል ነው:: ለበጎ ነገር መጨነቅና መጠበብን ማን ይጠላል? ዋናው አጨናነቁ ላይ ነው:: በራስ መተማመንን ስልቦ፣ ተስፋን በጣጥሶ፣ ብርሃንን አጨልሞ ለጥፋት እሚዳርግ ጭንቀት በሽታ ነው:: ከፍ ካለም ዕብደት ነው:: የዕብደትም አይነት አለው:: ለሰው መጨነቅና በሰው መጨነቅ እንኳ እንደሚለያየው ሁሉ የጭንቀት ዓይነቱ ብዙ ነው:: ለማንኛውም ግን ጤናማና ጤናማ ያልሆነ ጭንቀት ብሎ ለሁለት መክፈል ይቻላል:: ተከፍሏልም::

ጭንቀት ፈልገነው ሳይሆን ሳንፈልገው እሚመጣ ነገር ነው:: እኛ እምንፈልገው ያሰብነው እንዲሳካ ያለምነው እንዲሟላ ነው:: ይህ ደግሞ የዋዛ አይደለም: ብዙ ነገሮች ቀጥ ብለው አልተፈጠሩም:: ጠመም ጠመም ብለው ነው:: ወይም «በየመንገዱ አጋጣሚዎች» የተሞሉ ናቸው:: «ድንገት» እሚለውን ቃል እንኳ ብንወስድ ድንገት ማግኘት ድንገት ማጣት፣ ድንገት መታመም ድንገት መሞት፣ ድንገት መገናኘት፣ ድንገት መጋጨት፣ ድንገት ለአደጋ መጋለጥ፣ ድንገት መዳን ፣ ወዘተ ድንገቶች አሉ:: ሕይወት ድንገት በድንገት ነች:: ቢያንስ ለእነዚህ ድንገቶች በተጠንቀቅ መቆም ያስፈልገናል::

ለምሳሌ መታመም፣ መታረዝ፣ ለዕዳ መጋለጥ፣ ለድንገተኛ ዕርዳታ መዘገጃጀት ወዘተ ይኖራል:: የሻይ ጓደኛ፣ የፆታ ጓደኛ፣ የትዳር ጓደኛም ያጋጥማል:: ግጥምጥሞሹ ብዙ ነው:: ለዚህ ሁሉ ደሞ አስቀድሞ ገንዘብ ማስቀመጥ ያስፈልጋል:: እሚቀመጠው ገንዘብ ደሞ ከየት ይመጣል? ዛሬ ገንዘብ አየር ነው:: አለሱ አይተነፈስ:: እንደየሁኔታው መውጣት መውረድ ይኖራል:: መውጣት መውረድ ሲባል እንደፎቅ ደረጃ ዝም ብሎ እሚወጣበት ዝም ብሎ እሚወረድበት አይደለም:: አካል ብቻ ሳይሆን አዕምሮም አብሮ ይወጣል፣ አብሮ ይወርዳል:: ገደቧን ከጣሰች ወደ በሽታው ትለወጣለች::

በአጠቃላይ ለህይወት ጥሩ አመለካከት ቢኖረን እንኳ ከዚህ ከጤናማው ጭንቀት አናመልጥም:: እየመከትን እየተቋቋምን መንዝዝ የህይወት ግዴታችን ነው:: ፍሮይድ እሚለውም ይህንኑ ነው:: «ጭንቀትና ተቋቁሞው የኑሮ መሠረት ነው::»

ይህ ተቋቁሞው በተለያዩ መንገዶች ሊሆን እንደሚችልም ፍሮይድ አብሮ አብራርቷል:: እነዚህን መንገዶች «የተቋቁሞ ስልት (Defence Mecha-

nisms) በማለት ይጠሩቸዋል:: ሌሎች የሥነ ልቡና ጠበብትም «ጭንቀት» ለሚለው ቃል ያን ያህል ትኩረት ባይሰጡም በስልቶቹ ይስማማሉ:: በእነሱ እምነት እነዚህ ስልቶች (Coping) ማንኛውም ሰው ለሚገጥሙት ስነ ልቡናዊ ችግሮች መቋቋሚያነት የሚጠቀምባቸው ብቻ ሳይሆኑ ባህሪውንም እሚቀርጽባቸው ናቸው:: በዋና ዋናነት የተጠቀሱት የተቋቋሞ ስልቶችም የሚከተሉት ናቸው::

1. **Forgetting (Repression)** መርሳት ወይም መዘንጋት:: ይህ የተቋቋሞ ስልት ብዙዎቻችን እምንጠቀምበት ነው:: ልናነሳው ወይም እንዲነሳብን እማንፈልገውን ነገር፣ አውቀንም ይሁን ባለማወቅ እምንረሳበት ስልት ነው:: እማንወደው፣ እማንፈቅደው ነገር ወይም ትዝታን ወደድብቁ የአእምሮአችን ክፍል በመወሸቅ እንደሌለ ለማስመሰል እንጥራለን:: እሚቆረቁረንንና እሚከነክነንን ሀሳብ ከዕለት ተዕለቱ አእምሮአችን ለማፅዳት እንፈልጋለን:: እነዚህ አስጨናቂ ነገሮች ካልተጨቆኑ፣ ካልተዘነጉ አእምሯችን ጤና አያገኝም:: ብዙ ጊዜ «ዝጋው አባክህ!» መባሉም ለዚሁ ነው:: ለምሳሌ እስከዛሬ የተጨነቅንባቸውና የተበሳጨንባቸውን ነገሮች፣ እንኳን በቁጥር በዓይነት እንኳ አለማወቃችን አንዱ ማስረጃ ነው:: ሌላው ቀርቶ ለአእምሯችን ጤንነት (ምቾት) ስንል ከእማንፈልገው ሰው ጋር የነበረንን ቀጠሮ ልንረሳው እንችላለን:: የአንዳንድ ሰዎችንም ስም እዚያው አውቀን እዚያው እንረሳለን:: የተገኘውን ሁሉ የማስታወስ ልምዳችን እየቀነሰ ሊሄድ ይችላል:: ለነገሮች ደንታ ማጣት ይከተላል:: የተገኘውን ሁሉ ቅርቅር፣ ጥርቅም ማድረጉ ብዙ ጊዜ ጥሩ ላይሆን ይችላል::

2 **Reversing Motives (Reaction Formation)** የተገላቢጦሽ:: ይህ ስልት «መስበር ያቃተህን እጅ ሳመው» ከሚለው የአገራችን አባባል ጋር ይስማማል:: «ቀኝህን ሲመታህ ግራህንም ስጠው» የሚለውን ያህል የዋህ ስልት ባይሆንም ለራስ ደህንነት ሲባል እሚመረጥ የብልጠት ስልት ነው:: ከአቅም በላይ የሆነ አስጨናቂ ነገር ወይም ችግር ሲገጥም የተገላቢጦሹን መመለስ ማለት ነው:: በትንሿ ምሳሌ እንኳ ብንወስድ፣ በጥባጭና ከራሷም አልፎ መንደር ያስቸገረ ልጅ ያላት እናት፣ ልጁ ቢያበሳጫትም ልጅ ነውና አትጠላውም:: እንዲያውም የመጥላት ነገር ለምን ይነሳል? ትወደዋለች:: እሚያበሳጭን ነገር እየወደዱ መኖር ግዴታዋ ነው፣ የውዴታ ግዴታ:: «ላም እሳት ወልዳ እንዳትልሰው ፈጃት እንዳትተወው ...» ዓይነት ነገር መሆኑ ነው::

3 **Blaming Others (Projection)** ማላከክ:: ማሳበብ:: የአብዬን ወደ ዕምዬ ማድረግ:: ይህ ስልት የራሳችንን ጥፋትና ስህተት በሌሎች በማላከክ ከጭንቀታችን ለመገላገል እምንጠቀምበት ዘዴ ነው:: ይህ ባብዛኞቻችን ዘንድ የተለመደ ነገር ነው::

4 **Making Excuses (Rationalization)** ምክንያታዊነት:: ለተደቀነብን ችግር ለደረሰብን አደጋ ወይም ለገጠመን ውድቀት በምክንያት የተደገፈ ማረጋገጊያ እምናበጃጅበት ዘዴ ነው:: ጥፋተኛው እኛም እንሁን ሌላው አሳማኝና አረጋጊ ምክንያት እምናመቻችበት ስልት ነው:: ይህ ስልት ከወቀሳም ሆነ ከከሰሳ እሚያነፃ፣ ስህተተኝነትን ወይም ሽንፈትን (ለጊዜውም ቢሆን) ሙልጭ አድርጎ እሚያጥብ ሳሙና ነው:: አስተጣጠቡም ወይ በሳይንስ፣ ወይ በፍልስፍና (ሎጂክ)፣ ወይ በሥነልቡና ወዘተ... ገንዳ ሊሆን ይችላል:: ይሁን እንጂ ባብዛኛው በድብቁ የአእምሯችን ክፍል የሚከወን በመሆኑ የራስን እውነተኛ እንቅስቃሴ ለመከታተል አያስችልም:: ለምሳሌ በትምህርቱ የወደቀ ተማሪ አስተማሪ መሆን የቱን ያህል መጥፎ ነገር መሆኑን፣ ወይም የፈተና አወጣጡ ያልተስተካከለና መዛኝ አለመሆኑን ወዘተ አሳማኝ ምክንያቶችን (ምናልባትም መምህሩን ራሱ እሚያሳምኑ) መደርደር ይችላል:: በሌላም በኩል የራሱን ንዴት ልጁን በመቀጥቀጥ የተወጣ አባት ስህተተኛ መሆኑ ሲገባውም፣ መጨነቅ አይፈልግም:: ምኑ ሞኝ ነው:: «እንዲያውም እኮ ልጅን መቅጣት ለልጁ ለራሱ ጥሩ ነው::» እሚል ድንቅ ምክንያት ወዲያው ከች ሊልለት ይችላል::

5 **Kiking the d0g (Displacement)** «አህያውን ፈርቶ ዳውላውን» እምትለዋ ተረት ለዚህ ስልት በቂ ምሳሌ ነች:: አለቃው ያንቋረጠጡት ሠራተኛ ቤት ገብቶ ሚስቱ ላይ ዘራፍ ይላል:: ካለበለዚያ ማን ሲበሳጭ ይውላል:: ንዴት ቶሎ መብረድ አለበት:: ሚስትም ምኗ ሞኝ ነው? ሠራተኛዋን ከንዴቱ ታቋድሳታለች:: ሠራተኛም በተራዋ ግቢ ውስጥ ላለው ውሻ ፍልጥ ቢጤ ታቀምሰዋለች:: እንዲያ እንዲያ እየተባለ ዳውላ ዳውላው ይወቀጣል:: አህያ አህያውንማ ማን ነክቶት?

6 **Identification-** ኩረጃ:: ለገጠመን ችግር እንደማካካሻነት ከምንጠቀ ምባቸው ስልቶች አንዱ ኩረጃ ወይም ሌሎችን የመምሰል ዘዴ ነው:: በተለይ ታዋቂ የሆኑ ሰዎችን አርአያነት መከተልና ከእነሱም ጋር ጉድኝት በመፍጠር ሌላ ዕውቅና ለመፍጠር መዘገጃጀት የዚህ ዘዴ አንዱ ባህርይ ነው:: የሚደገፉትን ግለሰብ ወይም ቡድን ድልም ሆነ ጠንካራ ጐን ወስዶ መኩራራትም

የዚህ ስልት ውጤት ነው:: ይህ ስልት ምናልባትም ደግ ደጉን ከተቀሰመለት ጠቃሚ መሆኑ አይካድም:: ይሁን እንጂ በደፈናው እንደሚያደንቁት ሰው መልበስ፣ መናገር አልፎም ለመኖር መጣር እኔነትን ሊያስረሳ ይችላል:: ያልተሳካውን እኔነት በሌላ ማንነት ለመተካት መሞከር የሰው ወርቅ ነውና አያደምቅም፣ ለንቦጭን ጥሎ

7 Fantasy (Daydreaming) ይህ ደግሞ ከዕውነተኛው የሕይወት ገፅታ ወጣ ብሎ ለራስ ብቻ ከተፈጠረው የሕልም ዓለም ለአፍታ ያህል ሽርሽር ብሎ እሚመጣበት ስልት ነው:: በዚህ የምናብ ዓለም ነገሮች ሁሉ ቀጥ ብለው ሲሄዱ ይታዩናል:: ያሰብነው ያቀድነው ሁሉ በቀላሉ ሲፈፀም ወለል ብሎ ይታየናል:: ድል በድል ያንበሸብሹናል:: እንዲያውም ሊያስጨንቀን የቃጣው ችግር እስኪያስፈግገን ድረስ እጅግ በጣም ቀላል መስሎ ይታየናል:: ከፍ ካለም በመቻገራችን ራሱ ደስ ሊለን ይችላል: ራስን ከፍ ከፍ አድርጎ ማየት፣ በራስ መኩራራት ገደቡ ከፍ ይላል:: ይህ በብዙዎቻችን እሚዘወተር ነው:: በተለይ በወጣትነት ዕድሜ ክልል ውስጥ ባሉት ይጎላል:: በአጭሩ ይኽ ስልት ከዕውነታው ዓለም በምናብ ወደፈጠርነው ዓለም፣ እሚያስፈረጥጠን የፈጣን ደርሶ መልስ መንገድ ነው ማለት ይቻላል:: እንኳን በችግር ጊዜ በደህናውም ጊዜ ቢሆን፣ በምናብ ተንሸርሽሮ፣ በምኞት ተናፍሶ መምጣትን ማን ይጠላል? ችግሩ «አፈር ነህና ...» ሆነ እንጂ!

8 Acting Childish (Regression) ይህ የተቋቁሞ ስልት ባብዛኛው በህፃናት፣ በተለይም 4 ወይም 5 ዓመት አካባቢ ባሉት ላይ ይታያል:: ይህም የሆነበት ምክንያት ይህ ወቅት ሕፃናት ከነገሮች ጋር መጋፈጥ እሚጀምሩበትና የሀሳብ ሙግት እሚገጥሙበት በመሆኑ ነው:: የጭንቀቱ ምንጭ የተለያየ ቢሆንም፣ የመጨረሻ ልጅነትን፣ ወይም ብርቅዬነትን የሚነጥቅ ልጅ ከተወለደ ቅናትም ያስከትላል:: በተለይ በዚህ ክልል ባሉት ሕፃናት ላይ መቀናናቱ ተዘውትሮ እሚታይ ነው:: አዋቂዎችም ቢሆኑ ከዚሁ ስልት አያመልጡም:: እንደ ልጅ አባብሉኝ ማለት ወዘተ በመጠቀም ለተጨነቁባቸው ነገሮች ማካካሻ ወይም ማስረሻ ይፈልጋሉ:: እንደ ልጅ «ምን ሆነሃል? ምን ነካህ?» መባል አንዳንዴ አዋቂዎችንም ሲያስደስት እሚታየውም ለዚህ ነው::

9 Sublimaton & Compensation ማካካስ ወይም ማጣጣት:: በአንድ መንገድ አልሳካ ያለውን ሌላ አማራጭ በመሻት መጣጣር ያለ ነው:: ስሜት ከወደቀበት እንዲንሰራራ «ደካማ ጐኔ ይህ ነው» ተብሎ የታቀደበትን አቅጣጫ ሁሉ በሌላ ጠንካራ ጐኔ (ጊሬ ለመድፈንም) እሚዳርግ ዘዴ ነው:: ይህ በብዙዎች ዘንድ ይዘወተራል: ለምሳሌ የሰውነት አቋሙም ሆነ መልኩ፣ ወይም የኑሮ ደረጃው እማያወላዳ የመሰለው ሰው ተፈላጊነትን ለማትረፍ ሲል እሳት የላስ ፀሐፊ፣ ደራሲ፣ ስፖርተኛ ወይም ዕውቅ ሰው ለመሆን ይጣጣራል:: ተማሪም ከሆነ የማዕረግ ተማሪ በመሆን ተደናቂነትን ለማትረፍ ይጥራል:: የሒሳብ ትምህርት አልቀና ያለው ካለም በቋንቋ ጥይት ሆኖ ይቀርባል:: አይነ ግቡ ሆና የተፈጠረች ያልመሰላትም ሴት፣ የጨርቃጨርቅ መአት ብትከምር፣ የጌጥ ዓይነት ብትደረድር፣ በአነጋገሯ ብትዘምር ነገሩ ሌላ ሳይሆን የፉንጋነት ማባረሪያውና ማካካሻው ስልት ሊሆን ይችላል:: ድክመቱንና ጭንቀቱን ሁሉ በገንዘብ ኃይል ለማጣጣት እሚደክምም ብዙ ነው:: ብቻ ሕይወት በብዙ ማካካሻና ማጣጣጫ ስልቶች የተሞላች ነች:: ይህ ስልት ምናልባት ትንሽ ድካም እሚጠይቀውን የተሰጥኦ የድግግሞሽ ኩርኮራ ሊያዳክም ስለሚችል መጠንቀቁ አይከፋም:: አንድ ገጽ ጭሮ እምቢ አለኝ በማለት ወደ ጋራዥ መሮጥ ዕውቅ ሜካኒክ ለመሆን ከመቸኮል ሁለተኛዋን ገጽ ደግሞ መሞከሩ ሳይሻል አይቀርም:: ማን ያውቃል?

በአጠቃላይ በህይወት እንቅስቃሴ ውስጥ ሁሉንም ነገር በአሸናፊነት ለመወጣት አይቻልም:: ህይወት እያሸነፉም እየተሸነፉም፣ እየተነሱም እየወደቁም እሚጓዙባት መንገድ ነች:: ቀን እየተራባ እንደሚሄደው ሁሉ ፍላጐትም ይራባል:: ዋናው የአረባቡ ጉዳይ ነው:: ከአቅም በላይ ፍላጐት በፍላጐት ምኞት በምኞት መጥለቅለቁ ዋኝቶ ለመውጣት ያስቸግራል:: ችግሩም ያስጨንቃል:: በአልሞት ባይ ተጋዳይነት ጭንቀተን እየገደሉ መሄድ አስፈላጊ ነው:: አገዳደሉም ባብዛኛው ከላይ በተዘረዘሩት የተቋቁሞ ስልቶች እሚከወን ነው:: ይሁን እንጂ ችግርን መግደልና መደለል ይለያያል::

እነዚህ የተቋቁሞ ስልቶች ለጥቃቅን ችግሮች በመጠቀም ጊዜያዊ እፎይታ ማግኘቱ ጥሩ ሊሆን ይችላል:: ማንንም ለጉዳት ሳይሰጥ ከችግር የማምለጫ ዘዴ መስሉም አይታይም ይሆናል:: ይሁን እንጂ ተከታታይነትና ቋሚነት ባህርይ ያላቸውን ችግሮች ለዘለቄታው ለመፍታት አያስችሉም:: ከዕውነተኛ የችግሮች ምንጭ ጋር ፊት ለፊት አያጋፍጡም:: ሁሌም አሳማኝና ትክክል መፍትሔ አያስገኙም:: ይህ ከሆነ ደግሞ ዛሬ የተድበሰበሰው ችግር ነገ ወጣ ማለቱ አይቀርም:: ስለዚህም ለራስ ስህተትና ችግር እምንሰጠው መፍትሔም ሆነ፣ እምንመርጠው የተቋቁሞ ስልት የቱን ያህል ዘለቄታዊነትና ዕውነተኛነት እንዳለው መሻቱ አይከፋም::



የዚህ ስልት ውጤት ነው:: ይህ ስልት ምናልባትም ደግ ደጉን ከተቀሰመለት ጠቃሚ መሆኑ አይካድም:: ይሁን እንጂ በደፈናው እንደሚያደንቁት ሰው መልበስ፣ መናገር አልፎም ለመኖር መጣር እኔነትን ሊያስረሳ ይችላል:: ያልተሳካውን እኔነት በሌላ ማንነት ለመተካት መሞከር የሰው ወርቅ ነውና አያደምቅም፣

7 **Fantasy (Daydreaming)** ይህ ደግሞ ከዕውነተኛው የሕይወት ገፅታ ወጣ ብሎ ለራስ ብቻ ከተፈጠረው የሕልም ዓለም ለአፍታ ያህል ሽርሽር ብሎ እሚመጣበት ስልት ነው:: በዚህ የምናብ ዓለም ነገሮች ሁሉ ቀጥ ብለው ሲሄዱ ይታዩናል:: ያሰብነው ያቀድነው ሁሉ በቀላሉ ሲፈፀም ወለል ብሎ ይታየናል:: ድል በድል ያንበሸብሹናል:: እንዲያውም ሊያስጨንቀን የቃጣው ችግር እስኪያስፈግገን ድረስ እጅግ በጣም ቀላል መስሎ ይታየናል:: ከፍ ካለም በመቸገራችን ራሱ ደስ ሊለን ይችላል፡ ራስን ከፍ ከፍ አድርጎ ማየት፣ በራስ መኩራራት ገደቡ ከፍ ይላል:: ይህ በብዙዎቻችን እሚዘወተር ነው:: በተለይ በወጣትነት ዕድሜ ክልል ውስጥ ባሉት ይጎላል:: በአጭሩ ይኸ ስልት ከዕውነታው ዓለም በምናብ ወደፈጠርነው ዓለም፣ እሚያስፈረጥጠን የፈጣን ደርሶ መልስ መንገድ ነው ማለት ይቻላል:: እንኳን በችግር ጊዜ በደህናውም ጊዜ ቢሆን፣ በምናብ ተንሸርሽሮ፣ በምኞት ተናፍሶ መምጣትን ማን ይጠላል? ችግሩ «አፈር ነህና ...» ሆነ እንጂ!

8 **Acting Childish (Regression)** ይህ የተቋቋሞ ስልት ባብዛኛው በህፃናት፣ በተለይም 4 ወይም 5 ዓመት አካባቢ ባሉት ላይ ይታያል:: ይህም የሆነበት ምክንያት ይህ ይህም የሆነበት ምክንያት ይህ ወቅት ሕፃናት ከነገሮች ጋር መጋፈጥ እሚጀምሩበትና የሀሳብ ሙግት እሚገጥሙበት በመሆኑ ነው:: የጭንቀቱ ምንጭ የተለያየ ቢሆንም፣ የመጨረሻ ልጅነትን፣ ወይም ብርቅዬነትን የሚነጥቅ ልጅ ከተወለደ ቅናትም ያስከትላል:: በተለይ በዚህ ክልል ባሉት ሕፃናት ላይ መቀናናቱ ተዘውትሮ እሚታይ ነው:: አዋቂዎችም ቢሆኑ ከዚሁ ስልት አያመልጡም:: እንደ ልጅ ለንቦጭን ጥሎ አብብሉኝ ማለት ወዘተ በመጠቀም ለተጨነቁባቸው ነገሮች ማካካሻ ወይም ማስረሻ ይፈልጋሉ:: እንደ ልጅ «ምን ሆነሃል? ምን ነካህ?» መባል አንዳንዴ አዋቂዎችንም ሲያስደስት እሚታየውም ለዚህ ነው::

9 **Sublimaton & Compensation** ማካካስ ወይም ማጣጣት:: በአንድ መንገድ አልሳካ ያለውን ሌላ አማራጭ በመሻት መጣጣር ያለ ነው:: ስሜት ከወደቀበት እንዲንሰራራ «ደካማ ጐኔ ይህ ነው» ተብሎ የታቀደበትን አቅጣጫ ሁሉ በሌላ ጠንካራ ጐኔ (2ረ ለመድፈን) እሚዳርግ ዘዴ ነው:: ይህ በብዙዎች ዘንድ ይዘወተራል፡ ለምሳሌ የሰውነት አቋሙም ሆነ መልኩ፣ ወይም የኑሮ ደረጃው እማያወላዳ የመሰለው ሰው ተፈላጊነትን ለማትረፍ ሲል እሳት የላሰ ፀሐፊ፣ ደራሲ፣ ስፖርተኛ ወይም ዕውቅ ሰው ለመሆን ይጣጣራል:: ተማሪም ከሆነ የማዕረግ ተማሪ በመሆን ተደናቂነትን ለማትረፍ ይጥራል:: የሒሳብ ትምህርት አልቀና ያለው ካለም በቋንቋ ጥይት ሆኖ ይቀርባል:: አይነ ግቡ ሆና የተፈጠረች ያልመሰላትም ሴት፣ የጨርቃጨርቅ መአት ብትከምር፣ የጌጥ ዓይነት ብትደረድር፣ በአነጋገሯ ብትዘምር ነገሩ ሌላ ሳይሆን የፉንጋነት ማባረሪያውና ማካካሻው ስልት ሊሆን ይችላል:: ድክመቱንና ጭንቀቱን ሁሉ በገንዘብ ኃይል ለማጣጣት እሚደክምም ብዙ ነው:: ብቻ ሕይወት በብዙ ማካካሻና ማጣጣጫ ስልቶች የተሞላች ነች:: ይህ ስልት ምናልባት ትንሽ ድካም እሚጠይቀውን የተሰጥኦ የድግግሞሽ ኩርኮራ ሊያዳክም ስለሚችል መጠንቀቁ አይከፋም:: አንድ ገጽ ጭሮ እምቢ አለኝ በማለት ወደ ጋራዥ መሮጥ ዕውቅ ሜካኒክ ለመሆን ከመቸኮል ሁለተኛዋን ገጽ ደግሞ መሞከሩ ሳይሻል አይቀርም:: ማን ያውቃል?

በአጠቃላይ በህይወት እንቅስቃሴ ውስጥ ሁሉንም ነገር በአሸናፊነት ለመወጣት አይቻልም:: ህይወት እያሸነፉም እየተሸነፉም፣ እየተነሱም እየወደቁም እሚጓዙባት መንገድ ነች:: ቀን እየተራባ እንደሚሄደው ሁሉ ፍላጐትም ይራባል:: ዋናው የአረባቡ ጉዳይ ነው:: ከአቅም በላይ ፍላጐት በፍላጐት ምኞት በምኞት መጥለቅለቁ ዋጋቶ ለመውጣት ያስቸግራል:: ችግሩም ያስጨንቃል:: በአልሞት ባይ ተጋዳይነት ጭንቀተን እየገደሉ መሄድ ግም አስፈላጊ ነው:: አገዳደሉም ባብዛኛው ከላይ በተዘረዘሩት የተቋቋሞ ስልቶች እሚከወን ነው:: ይሁን እንጂ ችግርን መግደልና መደለል ይለያያል::

እነዚህ የተቋቋሞ ስልቶች ለጥቃቅን ችግሮች በመጠቀም ጊዜያዊ እፎይታ ማግኘቱ ጥሩ ሊሆን ይችላል:: ማንንም ለጉዳት ሳይሰጥ ከችግር የማምለጫ ዘዴ መስሎም አይታይም ይሆናል:: ይሁን እንጂ ተከታታይነትና ቋሚነት ባህርይ ያላቸውን ችግሮች ለዘለቄታው ለመፍታት አያስችሉም:: ከዕውነተኛ የችግሮች ምንጭ ጋር ፊት ለፊት አያጋፍጡም:: ሁሌም አሳማኝና ትክክል መፍትሔ አያስገኙም:: ይህ ከሆነ ደግሞ ዛሬ የተድበሰበሰው ችግር ነገ ወጣ ማለቱ አይቀርም:: ስለዚህም ለራስ ስህተትና ችግር እምንሰጠው መፍትሔም ሆነ፣ እምንመርጠው የተቋቋሞ ስልት የቱን ያህል ዘለቄታዊነትና ዕውነተኛነት እንዳለው መሻቱ አይከፋም::



# «እፎይታ

ሒሳዊ ግምገማ

(ከካህሳይ ገብረእግዚአብሄር)

እፍታ በፋና ዴሞክራሲ አሳታሚ ታትማ ባለፈው ወርሀ ጥቅምት ለንባብ የበቃች የብዕር እሸት ናት:: እፍታ በውስጧ የያዘቻቸው ርዕሰ ጉዳዮች (በአሳታሚው አባባል ትረካዎች) በርካታ በመሆናቸው በእያንዳንዱ ላይ ጥልቅ ግምገማ ለማካሄድ አይመችም:: በአጠቃላይ መልኩ ግን መፅሀፏን በአምስት ምድቦች ከፍሎ (ልብ ወለድ፣ ወግ ስራ፣ ትርጉም፣ እውነተኛ ታሪክ፣ መጣጥፍ፣ ወግ፣ ስነ ግጥምና ካርቱን) ማየት ይቻላል::

የእፍታን ውስጣዊ ይዘት ከመፈተሻችን በፊት ግን ስለመፅሀፏ ሽፋንና ስያሜ ትንሽ ማለት ያስፈልገናል:: እፍታ ለምን እፍታ ተባለች? የመፅሀፏ ስያሜ (ርዕስ) እፍታ ተብሎ ለምን እንደተሰየመ የሚያውቁት አሳታሚዎቹ ቢሆኑም ከመፅሀፏ ይዘትና መልክ ተነስቶ አንዳንድ ነጥቦችን ማለት ይቻላል:: እፍታ 29 ጋዜጠኞችና ደራስያን ስራዎች ስብስብ ናት:: እፍታ ከአሁን በፊት በሀገራችን ከታተሙት 'መድብሎች' የሚለያት ግን የበርካታ ብዕረኞች 'እስትንብስ' በመሆንዋ ብቻ አይደለም:: እፍታ ትርጉምና ወጥ ልብወለድ ድርሰቶችን፣ መጣጥፎችን፣ እውነተኛ ታሪኮችን፣ ግጥሞችን፣ ካርቱኖችን አጣምራና አጣጥማ የያዘች የብዕር እንጉቻም ናት:: በሌላ በኩል እፍታ ከታላቁ የጥበብ ባህር ተጨልፋ የወጣች የስነ ፅሁፍ ጠብታ ናት:: በእነዚህና በሌሎች ምክንያቶች መፅሐፉ እፍታ ተብላ ተሰይማ ከሆነ 'በዳቦው ቆረሳ' ስነ ስርዓት ላይ ባንገኝም እንስማማለን::

ከስያሜው ጋር አብሮ መነሳት ያለበት በመፅሀፏ ሽፋን ላይ ያረፈው ምስል (ዲዛይን) ነው:: አልፎ አልፎ እንደምናየው በየመፅሀፉ ሽፋን ላይ የሚያርፈው ምስልና በውስጡ ያለው ይዘት የቁጣና የቋንጣ ያህል ይራራቃል:: እንዲያውም አንዳንዴ 'መልከጥፉን በስም ይደግፉ' የሚለውን ሀገርኛ ምሳሌ እንድናስታውስ ነው የሚያስገድዱን::

እፍታስ በዚህ በኩል እንዴት ትታያለች? ገና መፅሀፏን ሲያዩ (ከውጭ) ዓይንም የሚያርፈው የነግህ (አፈ-ፅባህ) ምስል በሆነው የአማኑኤል ፒፒና የፈጠራ ስራ ላይ ነው:: ፀሐይ የሌሊቱን ጨለማ እየጣሰች በአድማስ ላይ ብቅ ስትል፣ መሬት ጥቁር ድባብዋን ጥላ የብርሃን ልብስዋን ስትጎናፀፍ የሚያሳይ ተምሳሌት፣ የጉህ፣ የፅባህ፣ የነግህ ምስል:: ነግህ ደግሞ የቀን መጀመሪያ የብርሃን ማብሰሪያ ሰዓት ስለሆነ 'እፍታ' የሚለው ቃል ከምስሉ ጋር የሰምና የፈትል ያህል ዝምድና አለው::

ስለ እፍታ ውጫዊ ገፅታ ይህን ያህል ካልን ይበቃናል:: ከመግቢያው ለመጠቆም እንደተሞከረው እፍታን የምንዳስሳት በአምስት ክፍሎች በመሸንሸን ነው::

## 1. ልብ - ወለድ

በእፍታ ውስጥ ካሉት 44 ርዕሶች ውስጥ ወደ ግማሽ ያህሉ (ሃያዎቹ) የልብ ወለድ ስነ ፅሁፎች ናቸው:: ከእነዚህ መካከል ዘጠኙ ወጥ (የደራስያኑ የፈጠራ ውጤቶች) ስራዎች ሲሆኑ አስራ አንዱ ከባህር ማዶ ድርሰቶች የተተረጎሙ ናቸው:: በመሆኑም በልብ ወለድ ስር የታቀፉትን ርእሶች በሁለት ከፍለን እናያቸዋለን::

**ሀ/ ወጥ ልብ ወለድ ስራዎች፣** በዚህ ክፍል ውስጥ ከተካተቱት ድርሰቶች ሶስት ሶስት ፅሁፎችን በማቅረብ «የዝሆን ድርሻቸውን» የወሰዱት ተስፋዬ ገብረአብና ስብሀት ገብረእግዚአብሄር ናቸው:: የሺጥላ ኮከብ፣ ባሳዝን ደርቤና ይሁን እንደሻው እያንዳንዳቸው አንዳንድ ድርሰቶች አበርክተዋል::

ተስፋዬ ገብረአብ የእድሩ ስም ጠሪ የሚለው ድርሰቱ በእውነት የተፈፀመ ድርጊት መሆኑን ገና ከመግቢያው ቢነግረንም አቀራረቡ ከልብ ወለድ የስነ ፅሁፍ ክልል የሚዘል አይደለም:: ዋናው ነገር ተስፋዬ ራሱ የፈጠራቸው ይሁን እውነተኛው የልደታ ባሻ መላኩ የአብዛኛዎቹ የእድር ስም ጠሪዎችን ባህርይ የሚያሟሉ ናቸው::

ቁም ነገሩ ተስፋዬ ገብረአብ በዚህ ፅሁፉ እድሮቻችን የሞተን በራፍ ለመንካት ስንዝር ተከንድ ያህል ርቀት በቀራቸው ሰዎች «ሙታንን ለመሸኘት» የተዋቀሩ፣ በፈቃደኝነት ሽፋን በውዴታ ግዴታ የተተበተቡ ሰዎች ስብስብ መሆናቸውን ቁልጭ አድርጉ ለማሳየት የመቻሉ ጉዳይ ነው::




የእድር አባላት በህይወት እያሉ ሲታመሙና ሲቸገሩ አባላቱ ሊረዱዋቸው ቀርቶ የትአሉ? እንዴት ናቸው? እንደማይልዋቸው፣ ሌላው ቀርቶ እድርተኞቹ እነማን እንደሆኑ በግእዙ መዝገብ በስተቀር አመራሮችም ቢሆኑ ለይተው እንደማያውቁዋቸው፣ ጡሩንባ ካልተነፋ፣ እሪታና ለቅሶ ካልተሰማ፣ በስተቀር ከተሜው ከጐኑ ማን እንዳለ እንኳ እንደማያውቅ ነው ተስፋዬ ሊነግረን የፈለገው በአንፃሩ እድሮች 'በሙታን ለሙታን' ከመሆን አልፈው ለህያውያንም በሚበጅ መልኩ መደራጀት እንደሚገባቸው በሰምና ወርቅ መልዕክቱ፣ በብዕር ቀስቱ ያመለክተናል::

የተሻለ ኑሮ ፍለጋ ሌላዋ የተስፋዬ ገብረአብ የብዕር ውልድ ናት:: ደራሲው በአንድ በኩል ሰለጠን፣ ተማርን የሚሉ ከተሜዎች ለዘላቂ ፍቅርና ለገንዘብ ያላቸውን አመለካከት፣ በሌላ በኩል ያላቻ ጋብቻ የሚያስከትለውን ጠንቅ፣ በአጭር አገላለፅ ፍንትው አድርጐ ለማሳየት ችሏል:: ይሁንና ተስፋዬ የተሻለ ኑሮ ፍለጋ የምትለዋ ድርሰቱ እንደልቧ ለማደግ፣ ለመመንደግ የቦታ ጥበት አጋጥሟት ባለችበት እንደምትጥመለመል ሀረግ አምቆ ያስቀራት ነው የምትመስለው::

የተሻለ ኑሮ ፍለጋ የተሻለች፣ የሰፋች ምናልባትም ራስዋን የቻለች ረዥምም ልብወለድ መሆን ትችል ነበር::

በርሜሉ አይሞላም የደራሲው የብዕር ለዛ ይበልጥ ጉልቶ የታየበት ድርሰት ነው ማለት ይቻላል:: መልካቸው ከጠባያቸው፣ እውቀታቸው ከስራቸው ጋር ስለማይገናኝ የብዙ 'እስስቶች' ባህርይ በአንድ ማይክ ጨምቆ አቅምሶናል:: ትዳር፣ አማረኝ፣ አማረችኝ፣ አየኋት፣ አየችኝ ተብሎ የሚሰራ የሰንበሌጥ ዳስ ሳይሆን ከጥድና ከወይራ ማገር የሚሰራ ጠንካራ የህይወት ሽማ መሆኑን አሳይቶናል በብዕሩ:: ለጊዜያዊ ስጋዊ ፍላጐትና ለገንዘብ ተብሎ የሚመሰረት ትዳር የኋላ የኋላ ከኮሸሽላ እሾህ እንደ ተሰራ ፍራሽ የሚኮሰኩስ መሆኑንም ተስፋዬ አሳይቶናል::

ሶስቱ የስብሀት ድርሰቶችን አጣጥሞ ለመረዳት የደራሲውን የተለየ የብዕር ቋንቋ ማወቅ ሳያስፈልግ አይቀርም:: እንደተቀሩት ድርሰቶቹ ሁሉ ቢራቢሮ፣ ፊርአን ሲሶ ዝና፣ አጋፋሪ እንደሻውና አያድቡልቡሊም እንደ አንባቢው አመለካከት ሲመነዘሩ፣ ሲዘረዘሩ፣ ሲተረተሩ የሚችሉ በልዩ ብዕር ጥበብ ተከሽነው የቀረቡ የቀለም ልቃቂቶች ናቸው:: ፍልስፍናዊ ዘይቤአቸው፣ የሰምና ወርቅ ቃናቸው፣ የመመራመርና የማዝናናት ጠባያቸው ሳይረሳ ነው ታድያ::

የሺጥላ ኮከብና ባሳዝን ደርቤ በእንስሶቹ ቋንቋቸው የሰውን ድብቅ ባህርይና 'ስውር' ስራ አጉልተው፣ አሳይተውናል:: እያዝናኑ አስተምረውናል:: «... እናንተ ዘንድ ያለው ሁሉ እኛምጋ አለ:: እናንተም ትወልዳላችሁ፣ ትማራላችሁ፣ ትሞታላችሁ:: እኛስ ምን እያደረግን ያለን ይመስላችኋል? እኩል ነን:: ግን እኛ ታሪካችንን አናቆይም:: እንዳውም ታሪክ የምንለው ነገር የለም:: ልጠይቅህና የታሪክ ርባና ምኑ ላይ ነው? ለትምህርትነቱ እንዳትለኝ እስቃለሁ:: የምትማሩ ከሆነ አሁንስ ለምን ታጠፋላችሁ?» ይለናል አይጡ፣ ... ይጠይቀናል እኛን ሰዎቹን::

ትንሽ አለፍ ብሎ የሺጥላ በረዥሙ ሌሊት ያናገረው አይጥ እንዲህ ይላል «... ድንቄም ታሪክ! በዚህ ላይ ይህ ታሪክ እውነት ነው እንዲህ ውሸት ነው ትባባላላችሁ:: እኛ ግን እንዴት እዚህ ላይ እንደምንጣላ እውነት ነው፣ ይህኛው ተመልከት:: አይጦች ዘንድ እውነትና ሀሰት የለም:: እውነትን ስያሜ ሰጥቶ 'እውነት' ያሰኘው የእብለት መኖር ነው ...»

በመጨረሻ የሺጥላ ለአይጡም ለኛም ስለታሪክ ያለውን የራሱን አመለካከት ሰጥቷል:: የሚያረካ መልስ::

የባሳዝን ደርቤ 'ኩቲ' ከየሺጥላው አይጥ ጋር የሚጋራቸው በርካታ

# ዳይጀስት»

ጉዳዮች አሉ:: አይጡ የሺጥላን እንደሚሞግተው ሁሉ ኩቲም ባሳዝንን ይሞግተዋል፤ አንዳንዴም ይረታዋል:: «... ውሻ ከዳተኛ፣ ልክስክስ፣ ምናምንቴ ... እያላችሁ የመጥፎ ምሳሌ ታደርጉናላችሁ:: እናንተ ግን በእምነታችሁ ሸርታታነትና በጥቅም ፍለጋ በህይወታችሁ ጭምር ስትከዳዱ ወቃሽም ሆነ ሰዳቢ የለባችሁም እንጂ፣ በውሻ ፈንታ ወይም ከውሻ በላይ መረገምና መወገዝ የእናንተ እጣ ሊሆን በተገባ ነበር:: እኛ ውሾች ለድህም ሆነ ለሀብታም እኩል እናድራለን:: ፀጉረ ልውጥ ሲሆንብን በሁሉም ላይ እኩል እንጮሀለን እንጂ ... የክብር፣ የንቀት፣ የአድልዎ ቋንቋ ከኛ ሰፈር የለም» በማለት::

በተለይ መንግስቱ ኃይለማርያምን አስመልክቶ ከኩቲ 'በውሻኛ ቋንቋ' የተሰነዘሩ አስተያየቶች ከላይ ሲያዩዋቸው ፈገግ የሚያሰኙ ቢመስሉም ያለፈውን የከረፋ ስርዓት መሪ ማንነት ቁልጭ አድርገው የሚያሳዩ ናቸው::

... ኧረ ጉድ ነው! እንዴት መሪ ይፈረጥጣል? ... ፈሪፈሪውን በጥይት በልልኝ ... እያለ ፋከራው አገር ሲያደነቁር የከረመ ጀግና እንኳንስ የሰው ልጅ ውሻ በማይሰማው አሾላለክ ኰቴውን አጥፍቶ ፈረጠጠ ... ፍርሀት እስከ ደቡብ አፍሪካ ጫፍ ይዞት ነጐደ:: ከዚያም ወዲያ ርቆ ቢሸሽ ባልጠላ ነበር፤ መሬት ክብ ስለሆነች አዙራ አራት ኪሎ እንዳትመልሰው ፈርቶ እንጂ ... (ገፅ 262-263)

ኩቲ ውሻው በሰዎች ላይ ብቻ ሳይሆን በራሱም ላይ 'ግለ ሂስ' አካሂዷል:: «... ዛሬ እንደማየው ከኛ የማይሻሉ ሰዎች ነበሩ አገር ሲገዙ የኖሩት:: ታዲያ በዚያ የፍዳ ዘመን ከዛሬው በላይ መጮህ ነበረብኝ:: እንዲያ ባለማድረጌ ይቆጨኛል» ሲል:: በአጭሩ የባሳዝን ደርቤ ድርሰት የተዋጣለት ነው ማለት ይቻላል::

በወጥ ልብወለድ ከፈረጅኩዋቸው ድርሰቶች የይሁን እንደሻው አሞራው ሼህ አንዷ ነች:: አሞራው ሼህ የይሁን የስራ ውጤት ብትሆንም የስብሀት ገብረ እግዚአብሄር የአፃፃፍ ዘየ ያጠላባት ትመስላለች:: በሌላ በኩል ደራሲው በርእሱ ላይ ከአሞራው ሼህ ካስተዋወቀን በኋላ ቀሪው ጉዞ ግን 'ከአባ' ጋር ሲያንኳትተን ነው የሚውለው:: ሼህና መነኩሴን ለማገናኘት ያደረገው ሙከራ '00' ላይ እንዳያርፍ አድርጉት ይሆን?

## ለ. ትርጉም ስራዎች

የትርጉም ስራዎች የአምስት ተርጓሚዎች (ደራስያን) ውጤቶች ናቸው:: የትርጉም ስራዎች ከስነ ፅሁፍ ይዘታቸው አንፃር የተዋጣላቸው ናቸው ማለት ይቻላል:: ከቀረቡት የአስራ አንድ የትርጉም ስራዎች መካከል አምስቱን ያቀረበው መኩሪያ መካሻ በተለይ አጭርና ጥልቅ መልእክት በያዙ የአንቶን ቼኾቭ ስራዎች ላይ ያነጣጠረ ይመስላል:: መኩሪያ የተጠቀመበት የአተረጓጐም ስልት፣ የቋንቋ ቃናና አቀራረብ የባህር ማዶዎችን ገፀ ባህርያት የራሳችን፣ የጐረቤታችን፣ የጓደኞቻችን ያህል እንድናውቃቸው አድርጓል::

ቢሆንም የመኩሪያ የትርጉም ስራዎች በሙሉ ከአንድ ኩሬ ተቀድተው መቅረባቸው 'ዩኒፎርም' እንዲለበስ እንደተገደደ የፋብሪካ ሰራተኛ የአንባብያንን የቀለም ምርጫ አጣቦታል::

ትእግስት ሁሩይና አፈወርቅ ዘለቀ የመኩሪያን ባህርይ ይጋራሉ:: የትእግስት ሁሩይ ትርጉሞች ከማክሲም ጐርኪይ ፅሁፎች፣ የአፈወርቅ ዘለቀ ደግሞ ከአንቶን ቼኾቭ ድርሰቶች ተወስደው የተተረጐሙ ናቸው:: የቴዎድሮስ ሙላቱና የገበየሁ ዋለልኝ አንዳንድ የትርጉም ስራዎችም በእፍታ ውስጥ ተካተዋል::

አተርፍ ባይ ከሚለው የገበየሁ ዋለልኝ የትርጉም ስራ በስተቀር ቀሪዎቹ አስር ድርሰቶች ከሁለት ደራስያን (አንቶን ቼኾቭና ማክሲም ጐርኪይ) የተወሰዱ ናቸው:: ይህም በሀገራችን የልብወለድ ደራስያን እጥረት ብቻ ሳይሆን የተርጓምያን ችግር እንዳለም የሚያሳይ ይመስላል:: የፈጠራ ውጤቶቻችንን በግዴታ ማብዛት ባይቻለንም ትርጉምን በተመለከተ ግን እፍታ ከዚህ የተሻለ ይዘት ይዛ መቅረብ ነበረባት:: ከአውሮጳ፣ ከአሜሪካ፣ ከላቲን አሜሪካ ደራስያን ውጤቶች ቆንጠር ቆንጠር አድርጐ ማቅረብ ይቻላል:: እፍታ በእፍታነትዋ ስትቀጥል ይህንን አስተካክላ መቅረብ ይጠበቅባታል::

## 2. እውነተኛ ታሪክ

በእፍታ ውስጥ በእውነተኛ ታሪክ ላይ የተመሰረቱ ዘጠኝ ትረካዎች እናገኛለን:: ከእነዚህ ድርሰቶት መካከል ኬጂቢ በአዲስ አበባ፣ የመንግስቱ አባት፣ የመንግስቱ አንጋች ትዝታና ትዳር በእደላ ባለፈው የደርግ ስርዓት ወቅት የተፈፀሙ ናቸው:: አራቱም በአራት የተለያዩ ፀሐፍት ነው የቀረቡት::

ሄኖክ ያሬድ ኬጂቢ በአዲስ አበባ በሚለው ትረካው በመንግስቱ ኃይለማርያም ይመራው የነበረው ስርዓት ሀገሪቱንና ህዝቦቿን ለጊዜያዊ ስልጣኑ ሲል በስውር እንዴት አሳልፎ ሰጥቷቸው እንደነበር ነግሮናል:: አርድቶናል ቢባል ሳይሻል ይቀራል?

አረፈዐይኔ ሀጐስ የመንግስቱን አባት አናግሮ የፃፈው ፅሁፉ አንባቢዎች ራሳቸው ከውይይቱ መሀል የነበሩ አይነት ሆነው እንዲሰማቸው የሚያደርግ አቀራረብ ነው:: የባሳዝን ደርቤ ኩቲ ስለመንግስቱ ያለው አባባል በእውኑ ዓለምም ከገዛ አባቱ ሲነገር እንሰማለን፤ እናነባለን፤ በአረፈዐይ ሀጐስ ፅሁፍ ላይ፣

«ቆራጡ መሪ እየተባለ ይወደስኩ ነበር»

«ለቆራጥነቱማ ቆራጥ ነው»

«እንዴት ማለት?»

«ክፉ ነዋ! ድንጋይራስ»

ከሁሉ በላይ የመንግስቱ ኃይለማርያም ማንነት አጉልቶ ያሳየን ግን አንጋቹ ነበር:: ማን ይናገር የነበረ ማን ያርዳ የቀበረ ነውና:: መንግስቱ ከመደበኛ ቢሮው ይልቅ በሰው ደም በተለሰነችው የምርመራ ክፍሉ ነበር ጊዜውን የሚያሳልፈው:: የሰው ደም እየመጠጠ የሰው አጥንት እየጋጠ የሚውልባት የሚያድርባትና የኖረባት የሲኦል ክፍል::

«ያቺ ምርመራ ክፍል ብሩህ አእምሮ ያለውን ስንቱን ወጣትና የተከተልነው መንገድ ትክክል አይደለም ብለው የተቃወሙ የደርግ አባሎችን እምሽክ አድርጋ የበላች ነች:: ... ወደዛች ክፍል ነበር መንግስቱ ዘልቆ የገባው:: ፍርደ ገምድሉ ዳኛና የሲኦል ቤቱ ተገናኙ:: አንድ መነፅር ያደረገና በውል የማላውቀው ሰው ለመንግስቱ አንድ ደብዳቤ ሰጠው:: መንግስቱ ወገቡ ላይ ከታጠቀው ሽጉጥ በተጨማሪ ብዕር መሰል ሽጉጥ ነበረውና በቀኝ እጁ የያዘውን ይህን ሽጉጥ ወደ ግራ እጁ አዛውሮ ለፊርማ ብዕሩን አወጣ:: ፊርማውንም አስቀመጠ፤ የሞት ፊርማ» (ገፅ 318-319)

መንግስቱ ጉደኛ ብዕር ብቻ አይደለም የነበረው 'መአተኛ' ከዘራም ነበረው:: ብዙዎቹ ፀረ አብዮተኞች የተባሉ የደርግ አባላትና ውድ የኢትዮጵያ ልጆች በዚች የዲያቢሎስ ከዘራ አማካኝነት ነበር ለህልፈት የተዳረጉት:: የመንግስቱ አንጋች እሸቱ ወንድሙ በዓይን ብሌኑ ያየውን በብዕሩ ካስቀመጠው በትንሹ እንመልከት::

«... መንግስቱ ድምፅ አልባውን ከዘራ እያነሳ ያነጣጥራል እንጂ በከዘራው አይማታም:: ያነጣጥራል:: ግንዱ ላይ እየመጡ የሚለጠፉት እስረኞች አሁንም ይወድቃሉ:: በጣም አነስተኛ የሆነ 'ጦሽ' የሚል የአለንጋ ድምፅ ሰማሁ:: በዚህ አይነት ኡደቱ ቀጠለ:: ... እኔ የማውቀው ከዘራ አባቶች ደከም ሲሉ ለምርኩዝነት የሚጠቀሙበትን እንጂ ከዘራው ድምፅ አልባ ጠመንጃ መሆኑን አላወቅሁም:: ራሴን ማመን አልቻልኩም:: ሆኖም ከስር ሰዎች ተረፍርፈዋል:: ያ ሰውበላ የቤተ መንግስት ቄሳር 'በከዘራው' ጉድ ሰርቶአቸዋል::»

የመንግስቱ አንጋች በዚች ኣጭር የምስክርነት ፅሁፉ መጨረሻ ያስተላለፋት መልዕክት አለች:: «እንዲህ አይነቱ አረመኔያዊ ድርጊት ወደፊት እንዳይደገም በመፈለጌ ነው ይህንን ምስክር መስጠቴ» የምትል:: በእርግጥም የእሸቱ ወንድሙ ምስክርነት ለትምህርትም፣ ለታሪክም ጠቀሜታዋ በእጅጉ የጐላ ነው::

ትዳር በእደላ (የአብዱል ቃድር አውልጃ ፅሁፍ) ሌላዋ የደርግን ስርዓት ምንነት ማሳያ መስተዋት ናት:: ደርግ በአንድ ወቅት በሺህ የሚቆጠሩ የትግራይና የወሎ አርሶ አደሮችን በግዳጅና በአፈና ከየቀያቸው እያፈናቀለ 'በሰፈራ' ሰበብ የአውሮና የበሽታ እራት ሆነው እንዲቀሩ ማድረጉ ይታወሳል:: ድርጊቱ ይፈፀም የነበረው በግዳጅ በመሆኑ ለሰፈራ ይወሰዱ የነበሩት የሚታረስ መሬት የሌላቸውና ስራ አጦች ብቻ አልነበሩም::

በአብዛኛው የደርግ ካድሬዎች አፈሳውን ያካሂዱ የነበረው በገበያ ቀን ስለነበር ሊያቀናም፣ ሊሸምትም የሄደው ሁሉ በጅምላ ይወሰድ ነበር:: በአንድ ወቅት አንቱ የተባለ ቱጃር ነጋዴ (አክሱም ከተማ) ገበያ እንደወጣ ታፍሶ አሶሳ መግባቱን የዚህ ፅሁፍ አቅራቢ ያውቃል::

የአብዱል ቃድር 'ትዳር በእደላም' ተመሳሳይ የሆነውን የደርግ የግፍ ተግባር ነው የምታሳየን:: በግዳጅ ለጦርነት መዝመት

# ዳይጀስት»

ጉዳዮች አሉ:: አይጡ የሺጥላን እንደሚሞግተው ሁሉ ኩቲም ባሳዝንን ይሞግተዋል፤ አንዳንዴም ይረታዋል:: «... ውሻ ከዳተኛ፣ ልክስክስ፣ ምናምንቴ ... እያላችሁ የመጥፎ ምሳሌ ታደርጉናላችሁ:: እናንተ ግን በእምነታችሁ ሸርታታነትና በጥቅም ፍለጋ በህይወታችሁ ጭምር ስትከዳዱ ወቃሽም ሆነ ሰዳቢ የለባችሁም እንጂ፣ በውሻ ፈንታ ወይም ከውሻ በላይ መረገምና መወገዝ የእናንተ እጣ ሊሆን በተገባ ነበር:: እኛ ውሾች ለድህም ሆነ ለሀብታም እኩል እናድራለን:: ፀጉረ ልውጥ ሲሆንብን በሁሉም ላይ እኩል እንጮሀለን እንጂ ... የክብር፣ የንቀት፣ የአድልዎ ቋንቋ ከኛ ሰፈር የለም» በማለት::

በተለይ መንግስቱ ኃይለማርያምን አስመልክቶ ከኩቲ 'በውሻኛ ቋንቋ' የተሰነዘሩ አስተያየቶች ከላይ ሲያዩዋቸው ፈገግ የሚያሰኙ ቢመስሉም ያለፈውን የከረፋ ስርዓት መሪ ማንነት ቁልጭ አድርገው የሚያሳዩ ናቸው::

... ኸረ ጉድ ነው! እንዴት መሪ ይፈረጥጣል? ... ፈሪፈሪውን በጥይት በልልኝ ... እያለ ፉከራው አገር ሲያደነቁር የከረመ ጀግና እንኳንስ የሰው ልጅ ውሻ በማይሰማው አሾላለክ ኰቴውን አጥፍቶ ፈረጠጠ ... ፍርሀት እስከ ደቡብ አፍሪካ ጫፍ ይዞት ነጉደ:: ከዚያም ወዲያ ርቆ ቢሸሽ ባልጠላ ነበር፤ መሬት ክብ ስለሆነች አዙራ አራት ኪሎ እንዳትመልሰው ፈርቶ እንጂ ... (ገፅ 262-263)

ኩቲ ውሻው በሰዎች ላይ ብቻ ሳይሆን በራሱም ላይ 'ግለ ሂስ' አካሂዷል:: «... ዛሬ እንደማየው ከኛ የማይሻሉ ሰዎች ነበሩ አገር ሲገዙ የኖሩት:: ታዲያ በዚያ የፍዳ ዘመን ከዛሬው በላይ መጮህ ነበረብኝ:: እንዲያ ባለማድረጌ ይቆጨኛል» ሲል:: በአጭሩ የባሳዝን ደርቤ ድርሰት የተዋጣለት ነው ማለት ይቻላል::

በወጥ ልብወለድ ከፈረጅኩዋቸው ድርሰቶች የይሁን እንደሻው አሞራው ሼህ አንዷ ነች:: አሞራው ሼህ የይሁን የስራ ውጤት ብትሆንም የስብሀት ገብረ እግዚአብሄር የአፃፃፍ ዘየ ያጠላባት ትመስላለች:: በሌላ በኩል ደራሲው በርእሱ ላይ ከአሞራው ሼህ ካስተዋወቀን በኋላ ቀሪው ጉዞ ግን 'ከአባ' ጋር ሲያንኳትተን ነው የሚውለው:: ሼህና መነኩሴን ለማገናኘት ያደረገው ሙከራ '00' ላይ እንዳያርፍ አድርጉት ይሆን?

## ለ. ትርጉም ስራዎች

የትርጉም ስራዎች የአምስት ተርጓሚዎች (ደራስያን) ውጤቶች ናቸው:: የትርጉም ስራዎች ከስነ ፅሁፍ ይዘታቸው አንፃር የተዋጣላቸው ናቸው ማለት ይቻላል:: ከቀረቡት የአስራ አንድ የትርጉም ስራዎች መካከል አምስቱን ያቀረበው መኩሪያ መካሻ በተለይ አጭርና ጥልቅ መልእክት በያዙ የአንቶን ቼኾቭ ስራዎች ላይ ያነጣጠረ ይመስላል:: መኩሪያ የተጠቀመበት የአተረጓጐም ስልት፣ የቋንቋ ቃናና አቀራረብ የባህር ማዶዎችን ገፀ ባህርያት የራሳችን፣ የጐረቤታችን፣ የጓደኞቻችን ያህል እንድናውቃቸው አድርጓል::

ቢሆንም የመኩሪያ የትርጉም ስራዎች በሙሉ ከአንድ ኩሬ ተቀድተው መቅረባቸው 'ዩኒፎርም' እንዲለበስ እንደተገደደ የፋብሪካ ሰራተኛ የአንባብያንን የቀለም ምርጫ አጣቦታል::

ትእግስት ህሩይና አፈወርቅ ዘለቀ የመኩሪያን ባህርይ ይጋራሉ:: የትእግስት ህሩይ ትርጉሞች ከማክሲም ጐርኪይ ፅሁፎች፣ የአፈወርቅ ዘለቀ ደግሞ ከአንቶን ቼኾቭ ድርሰቶች ተወስደው የተተረጐሙ ናቸው:: የቴዎድሮስ ሙላቱና የገበየሁ ዋለልኝ አንዳንድ የትርጉም ስራዎችም በእፍታ ውስጥ ተካተዋል::

አተርፍ ባይ ከሚለው የገበየሁ ዋለልኝ የትርጉም ስራ በስተቀር ቀሪዎቹ አስር ድርሰቶች ከሁለት ደራስያን (አንቶን ቼኾቭና ማክሲም ጐርኪይ) የተወሰዱ ናቸው:: ይህም በሀገራችን የልብወለድ ደራስያን እጥረት ብቻ ሳይሆን የተርጓምያን ችግር እንዳለም የሚያሳይ ይመስላል:: የፈጠራ ውጤቶቻችንን በግዴታ ማብዛት ባይቻለንም ትርጉምን በተመለከተ ግን እፍታ ከዚህ የተሻለ ይዘት ይዛ መቅረብ ነበረባት:: ከአውሮጳ፣ ከአሜሪካ፣ ከላቲን አሜሪካ ደራስያን ውጤቶች ቆንጠር ቆንጠር አድርጉ ማቅረብ ይቻላል:: እፍታ በእፍታነትዋ ስትቀጥል ይህንን አስተካክላ መቅረብ ይጠበቅባታል::

## 2. እውነተኛ ታሪክ

በእፍታ ውስጥ በእውነተኛ ታሪክ ላይ የተመሰረቱ ዘጠኝ ትረካዎች እናገኛለን:: ከእነዚህ ድርሰቶች መካከል ኬጂቢ በአዲስ አበባ፣ የመንግስቱ አባት፣ የመንግስቱ አንጋች ትዝታና ትዳር በእደላ ባለፈው የደርግ ስርዓት ወቅት የተፈፀሙ ናቸው:: አራቱም በአራት የተለያዩ ፀሐፍት ነው የቀረቡት::

ሄኖክ ያሬድ ኬጂቢ በአዲስ አበባ በሚለው ትረካው በመንግስቱ ኃይለማርያም ይመራው የነበረው ስርዓት ሀገሪቱንና ህዝቦቿን ለጊዜያዊ ስልጣኑ ሲል በስውር እንዴት አሳልፎ ሰጥቷቸው እንደነበር ነግሮናል:: አርድቶናል ቢባል ሳይሻል ይቀራል?

አረፈዐይኔ ሀጐስ የመንግስቱን አባት አናግሮ የፃፈው ፅሁፉ አንባቢዎች ራሳቸው ከውይይቱ መሀል የነበሩ አይነት ሆነው እንዲሰማቸው የሚያደርግ አቀራረብ ነው:: የባሳዝን ደርቤ ኩቲ ስለመንግስቱ ያለው አባባል በእውኑ ዓለምም ከገዛ አባቱ ሲነገር እንሰማለን፤ እናነባለን፤ በአረፈዐይ ሀጐስ ፅሁፍ ላይ፣

«ቆራጡ መሪ እየተባለ ይወደስኰ ነበር»

«ለቆራጥነቱማ ቆራጥ ነው»

«እንዴት ማለት?»

«ክፉ ነዋ! ድንጋይራስ»

ከሁሉ በላይ የመንግስቱ ኃይለማርያም ማንነት አጉልቶ ያሳየን ግን አንጋቹ ነበር:: ማን ይናገር የነበረ ማን ያርዳ የቀበረ ነውና:: መንግስቱ ከመደበኛ ቢሮው ይልቅ በሰው ደም በተለሰነችው የምርመራ ክፍሉ ነበር ጊዜውን የሚያሳልፈው:: የሰው ደም እየመጠጠ የሰው አጥንት እየጋጠ የሚውልባት የሚያድርባትና የኖረባት የሲኦል ክፍል::

«ያቺ ምርመራ ክፍል ብሩህ አእምሮ ያለውን ስንቱን ወጣትና የተከተልነው መንገድ ትክክል አይደለም ብለው የተቃወሙ የደርግ አባሎችን እምሽክ አድርጋ የበላች ነች:: ... ወደዛች ክፍል ነበር መንግስቱ ዘልቆ የገባው:: ፍርደ ገምድሉ ዳኛና የሲኦል ቤቱ ተገናኙ:: አንድ መነፅር ያደረገና በውል የማላውቀው ሰው ለመንግስቱ አንድ ደብዳቤ ሰጠው:: መንግስቱ ወገቡ ላይ ከታጠቀው ሽጉጥ በተጨማሪ ብዕር መሰል ሽጉጥ ነበረውና በቀኝ እጁ የያዘውን ይህን ሽጉጥ ወደ ግራ እጁ አዛውሮ ለፊርማ ብዕሩን አወጣ:: ፊርማውንም አስቀመጠ፤ የሞት ፊርማ» (ገፅ 318-319)

መንግስቱ ጉደኛ ብዕር ብቻ አይደለም የነበረው 'መአተኛ' ከዘራም ነበረው:: ብዙዎቹ ፀረ አብዮተኞች የተባሉ የደርግ አባላትና ውድ የኢትዮጵያ ልጆች በዚች የዲያቢሎስ ከዘራ አማካኝነት ነበር ለህልፈት የተዳረጉት:: የመንግስቱ አንጋች እሸቱ ወንድሙ በዓይን ብሌኑ ያየውን በብዕሩ ካስቀመጠው በትንሹ እንመልከት::

«... መንግስቱ ድምፅ አልባውን ከዘራ እያነሳ ያነጣጥራል እንጂ በከዘራው አይማታም:: ያነጣጥራል:: ግንዱ ላይ እየመጡ የሚለጠፉት እስረኞች አሁንም ይወድቃሉ:: በጣም አነስተኛ የሆነ 'ጦሽ' የሚል የአለንጋ ድምፅ ሰማሁ:: በዚህ አይነት ኡደቱ ቀጠለ:: ... እኔ የማውቀው ከዘራ አባቶች ደከም ሲሉ ለምርኩዝነት የሚጠቀሙበትን እንጂ ከዘራው ድምፅ አልባ ጠመንጃ መሆኑን አላወቅሁም:: ራሴን ማመን አልቻልኩም:: ሆኖም ከስር ሰዎች ተረፍርፈዋል:: ያ ሰውበላ የቤተ መንግስት ቂሳር 'በከዘራው' ጉድ ሰርቶአቸዋል::»

የመንግስቱ አንጋች በዚች አጭር የምስክርነት ፅሁፉ መጨረሻ ያስተላለፋት መልዕክት አለች:: «እንዲህ አይነቱ አረመኔያዊ ድርጊት ወደፊት እንዳይደገም በመፈለጌ ነው ይህንን ምስክር መስጠቴ» የምትል:: በእርግጥም የእሸቱ ወንድሙ ምስክርነት ለትምህርትም፣ ለታሪክም ጠቀሜታዋ በእጅጉ የጐላ ነው::

ትዳር በእደላ (የአብዱል ቃድር አውልጃ ፅሁፍ) ሌላዋ የደርግን ስርዓት ምንነት ማሳያ መስተዋት ናት:: ደርግ በአንድ ወቅት በሺህ የሚቆጠሩ የትግራይና የወሎ አርሶ አደሮችን በግዳጅና በአፈና ከየቀያቸው እያፈናቀለ 'በሰፈራ' ሰበብ የአውሮና የበሽታ እራት ሆነው እንዲቀሩ ማድረጉ ይታወሳል:: ድርጊቱ ይፈፀም የነበረው በግዳጅ በመሆኑ ለሰፈራ ይወሰዱ የነበሩት የሚታረስ መሬት የሌላቸውና ስራ አጦች ብቻ አልነበሩም::

በአብዛኛው የደርግ ካድሬዎች አፈሳውን ያካሂዱ የነበረው በገበያ ቀን ስለነበር ሊያቀናም፣ ሊሸምትም የሄደው ሁሉ በጅምላ ይወሰድ ነበር:: በአንድ ወቅት አንቱ የተባለ ቱጃር ነጋዴ (አክሱም ከተማ) ገበያ እንደወጣ ታፍሶ አሶሳ መግባቱን የዚህ ፅሁፍ አቅራቢ ያውቃል::

የአብዱል ቃድር 'ትዳር በእደላም' ተመሳሳይ የሆነውን የደርግ የግፍ ተግባር ነው የምታሳየን:: በግዳጅ ለጦርነት መዝመት

አልበቃቸው ብሎ ቤተሰቦቻችን፣ ልጆቻችን ናፈቁን ግዳጃችንን ከፈፀምን ወደቀያችን መልሱን፣ ካልሆነም ቤተሰቦቻችንን አምጡልን ላሉት አርሶ አደሮች የተሰጣቸው ምላሽ ሁለት ነበር: ለከፊሎቹ ጥይት፣ ለቀሩት ደግሞ 'ተመሳሳይ ሚስቶች'::

በሐረርና በድሬዳዋ ከተሞች «አስራ ሁለተኛ ክፍል የፈፀማችሁና ስራ አጥ የሆናችሁ ሴት ተማሪዎች ተመዝገቡ» የሚል ማስታወቂያ ይወጣል:: በሺህ የሚቆጠሩ ተመዘገቡ፣ ስራ ለመያዝ:: የደርግ ካድሬዎች የመሰልዋቸውን 'ኮረዶች' መረጡ:: ከተማሪዎች ሌላ የተወሰኑ ሴተኛ አዳሪዎችንም መለመሉ:: ሁሉንም አሳፍረው (አፍነው) ወደ ጐዴ ወሰዱዋቸው:: ከዚያም በአንድ በኩል ለዓመታት ከሚስቶቻቸው ተለይተው የቆዩትን ሚሊሺያዎች ሚስቶቻችሁን ይዘንላችሁ መጥተናልና ተሰልፋችሁ ተቀበሉዋቸው አሉዋቸው:: እያንዳንዱ ሚሊሺያ «ዛሬስ ደርግ እንዴት ደግ ሆነ?» እያለ ከሚስቱ ጋር ለመገናኘት በናፍቆት ይጠባበቅ ገባ:: በመጨረሻ ግን የደርግ ካድሬዎች ያልታሰበና ያልተጠበቀ ቲያትር ሰሩ:: ወታደሮቹ በሰልፍ እንደቆሙ አፍነው ያመጡዋቸውን ሴቶች እንደ ራሽን ብስኩት አንዳንድ አደልዋቸው:: ያለቤት፣ ያለቀለብ፣ ያለስርግ አጋቡዋቸው:: ብዙዎቹ በበረሃው ንዳድ በወባ በሽታ ተቀጥፈው ቀሩ:: ለታሪክ ምስክርነት የቀሩም አሉ:: አብዱል ቃድር በብዕሩ አጣፍጦ ያቀረበልን ይህንኑ መራራ እውነት ነው::

ከዚያው ከእውነተኛ የታሪክ ምዕራፍ ሳንወጣ ወደ እሸቱ ተፈራ ስራዎች እንሸጋገራለን:: እሸቱ ተፈራ በሞገደኛው ጋዜጠኛ የሚያወጋን ስለዝነኛው መንግስቱ ገዳሙ ነው:: መንግስቱ ገዳሙ እሸቱ እንዳለው በርካታ 'አስቂኝና አስገራሚ' ገጠመኞች የነበሩት አንጋፋ ጋዜጠኛ ነበር::

መንግስቱ አስቂኝና አስገራሚ ከሆኑት ድርጊቶቹ ጀርባ በአስተማሪነታቸው ትቶልን የሄደው ተመክሮዎቹም ቀላል አይደሉም:: እሸቱ ተፈራ መንግስቱን 'ከውስጥ' ጠልቶ ያውቀው እንደነበር ከፅሁፉ ማወቅ ይቻላል:: ስለመንግስቱ በዝና የሰሙ ብቻ ሳይሆኑ መንግስቱን በቅርብ እናውቀዋለን የሚሉ ሳይቀሩ የእሸቱ ተፈራን ፅሁፍ በጥሞና ማንበባቸው አይቀሬ ነው:: እሸቱ በዚህ ቀላልና ግልፅ በሆነ አቀራረቡ ለመንግስቱ ገዳሙ ትንሽ የመታሰቢያ የብዕር ሐውልት ሰርቶለታል ማለት ይቻላል::

«ሌባ ላሙሉና» «ማነው ንፁህ» የተሰኙት በእውነተኛ ታሪኮች የተመሰረቱ ፅሁፎችም ቢሆኑ እሸቱ ማራኪ በሆነ አገላለፅ እውነታን አጉልቶ የማሳየት ብቃቱ ያስመሰከረባቸው ስራዎቹ ናቸው::

አታክልት ሀገገ ደራርቱን የገለፀበት ብዕሩ ለሌሎች አንባብያን ብቻ ሳይሆን ለአትሌቷ ለራሷም ቢሆን ቋሚ ማስታወሻ ነው:: አታክልት በነካ እጁ የእኑ ኃይሌ ገብረስላሴንም ታሪክ ቢያቀምሰን መልካም ነው:: የጀቤ ምስጢር ምስጢርን እየወለደ ልቦናን በሀሳብ የሚያሸፍት አጓጊ ፅሁፍ ነው:: በኢትዮጵያ ውስጥ በርካታ 'ጀቤዎች' ስላሉ በቀጣዩ እፍታ የአንዳንዶችን ታሪክ እንጠብቃለን::

## መጣጥፍ (ወግ)

በዚህ የስነ ፅሁፍ ዘርፍ በአስር በሳል ብዕረኞች የተፃፉ አስራ አራት መጣጥፎች ተካተዋል:: ከአስራ አራቱ ርዕሶች በተስፋዬ ገብረአብ የቀረበችው የመቀሌ ቀልዶች «ድንቅዬዋ» ነች:: የደምሴ ፅጌ «መቼ ይሆን?» በመጠን መንትያ ትሆናለች::

የመቀሌ ቀልዶች ራስዋን ችላ የቀረበች ድርሰት ብትሆንም በውስጧ ስድስት ቀልዶችን ብቻ ነው የያዘችው:: እንደ አጋጣሚ ሆኖ ተስፋዬ በምንጭነት የተጠቀመባቸው «ቀልዶች» እያንዳንዳቸው የባለ መቶ ቀልዶች ምንጭ ናቸው:: ተስፋዬ ከጀመረው አይቀር ቢያንስ አንድ አስራ አምስት ያህል አቅርቦ ሊያስቀን ሲገባ በስድስት ቀልዶች ብቻ ቀልዶብን ቀርቷል::

ደምሴ ፅጌ ከእውነተኛ ገጠመኞቹ ተነስቶ በከሸናት «መቼ ይሆን?» መጣጥፉ በአጭር አገላለፅ ሰፊ መልዕክት የማስተላለፍ ችሎታውን አስመስክሮበታል::

ደረጀ ደስታ «በምንትሴ ቅብጥርሴ» በኪነት ጀልባ አሳፍሮ በጥበብ ባህር እንድንዋኝ ያደርገናል! አንዳንዴም በፈጠራው የብዕር ማዕበሉ ይንጠናል! ያናውጠናል::

«ራስ ለሆድ አሽከር ነው ይባላል»

«ቢሆንም ቢያንስ ቢያንስ?»

«ቢያንስ ምን?»

«ስለሆድ የሰበከ ሰው ...»

«ምን መሆን አለበት?»

«መሆን የሌለበትን ማወቅ አለበት»

«ካላወቀስ?»

«ይማራ!»

«ከነማን?»

«ከነወጋየሁ»

«እነሱማ ሞቱ»

«ብዙ ወጣቶችም እኮ አሉ»

«እነሱም ተዋጡ»

«በማን?»

«በሆዳሞች!» (ገፅ 93)

እያሌ ጥበብና ጥበበኞች እየገጠማቸው ስላለው እንቅፋትና ፈተና ያወሳል:: የማን ዘር ጐመንዘር ከጥሩ የቀለም ዘር የበቀለች የስነ ፅሁፍ ፍሬ ናት:: የአጉልተኞች አጉል ምኞትንና አስተሳሰብን አምክና ወደዋናው መስመር የምትመራ የጥበብ ቅያስ::

«... አፍሪካዊ ነኝ፣ ወይም ኢትዮጵያዊ ነኝ ወይም ትግሬ ነኝ፣ ወይም የጠራሁ አማራ ነኝ፣ ወይም በራሴ የገዳ ሲስተም አስተዳደር የኖርኩ የኮራሁ ኦሮሞ ነኝ ወዘተ ... መባሉ ብቻውን ምንም አይጠቅምም:: ዋናው ሆኖ መገኘት ነው::»

«... ልመናና ኩራትን እስከመቼ አብረን እንደምናስኬድ አይገባኝም:: ያውም በእኛ ሳይሆን በእነ ሉሲ እየኮራን:: ለማንኛውም ኩራት እራት አይሆንም እንዲሉ ቢያንስ ዛሬን እናሸንፋት:: አለበለዚያ አንዱ እንዳለው 'ዘርህን ገበያ ላከውና እሚገዛልህን እየው' እንዲባል ዘር ስንቆጥር ፀሐይ እንዳይጨልም:: እሱ ቀርቷል:: ሌላ ዘፈን መጥቷል:: የማንዘር ጐመን ዘር::»

ደረጀ በዚህ መጣጥፉ ለእያንዳንዳችን ዛሬ የሚያስፈልገን የስራ ውድድር የነበርኩ ነበርኩ ሳይሆን የነኝ ክርክር ነው» ነው የሚለን:: «አፈርና ሰው የአፈር ገፊውን ገበሬ ህይወት የምትዳስስ መጣጥፍ ናት:: አፈር ገፊው አፈር ምሶ፣ አፈር አለስልሶ፣ አፈር ለውሶ፣ አፈር ነስንሶ፣ አፈር በልቶ፣ አፈር ላይ ተኝቶ፣ በአፈርነቱ ኮርቶ፣ የሚኖረውን ገበሬ ልፋቱ፣ ጥረቱ፣ እንግልቱ? ከሁሉ በላይ ጥንካሬው፣ ብርታቱ፣ አይበገሬነቱ፣ ዋልታነቱ፣ የወገንና የሀገር ኩራትነቱን ያሳየናል ደረጀ::

በሌላ በኩል በአፈር ገፊ ጀርባ ታዝሎ የሚኖረው ከተሜን በማን ላይ ቆመሽ ማንን ታሚያለሽ» የሚለውን ገበሬኛ ምሳሌ ሳያጤን አፈር ለብሶ አፈር መመገቡን እየረሳ ገበሬውን መናቅና መራቅ እንደማይገባው፣ በብዕሩ ይነግረዋል፣ ይመክረዋል::

«ይህ አሜሪካ ነው» አሜሪካ ለመሄድ ዲቪ ፎርም በመሙላት የአዲስ አበባ ፖስታ ቤቶችን ሲያጣብቡ ለሚውሉ ወጣቶች አንዳች የምታስተላልፈው መልዕክት ይኖራታል::

አሜሪካ ውብም፣ አስቀያሚም፣ ደስ የምትል፣ አስጠሊታም፣ በአጭሩ አሜሪካ ሲኦልና ገነት አጠገብ ለአጠገብ የሚገኙባት ልዩ ቦታ ትመስላለች እንደ ተስፋዬ ገብረአብ አገላለፅ:: አሜሪካ የፈረንጅ ምስል ያለበት ቲሸርት ለብሰው ስለተንጐራደዱ፣ የሬጌና የሮክ የጭፈራ ስልቶች ስለቻሉ ብቻ ዶላር የሚታፈስበት አለመሆንዋን ነው የምንገነዘበው::

በአሜሪካ «የሰራ ይኖራል! ያልሰራ ይቀራል» በቃ ሌላ አማራጭ የለም:: አሜሪካ አሜሪካ የሆነችውም በስራ ብቻ ነው::

በሌላ በኩል አሜሪካ ውስጥ ሰው አብዛኛውን ጊዜውን የሚያሳልፈው በስራ በመሆኑ «ለማህበራዊ ኑሮ» የሚሆን ትርፍ ሰዓት የለውም:: በመሆኑም መጠያየቅ፣ አብሮ ቡና መጠጣት፣ ማውካካትና መተማማት ብሎ ነገር የለም:: ሁሉም ዶላር ለመቁጠር ነው ሩጫው::

«እያንዳንዱ የግለኝነት ርቾት በየቤቱ ይተኩሳል:: በሩን ዘግቶ ብቻውን ገንዘቡን ይቆጥራል:: ሚስቱንም ስለማያምናት ለኪሱ መቆለፊያ ጉዋጉንቸር ይገዛል:: ባልና ሚስት ገንዘብ ያዋጡና ማቀዝቀዣውን ይሞላሉ:: ቢታመሙም ከየራሳቸው ነው ከፍለው የሚታከሙት:: ልብሳቸውን ራሳቸው ይገዛሉ:: ቤት ኪራይ አዋጥተው ይከፍላሉ:: የደባል ያህል እንኳ መግባባት ያቅታቸዋል::»

«... አሜሪካ ውስጥ ገንዘብና ክብር ቢኖርም በጭንቀት የተሞሉ ሰዎች አያሌ ናቸው:: እንባ ከዓይናቸው የማይለይ ጥቂት አይደሉም:: በሚያጠራቅሙት ገንዘብ ይጨነቃሉ:: በባልና ሚስት

መካከል ያለው ትስስር የወሲብ ወይም የጥቅም እንጂ እውነተኛ ፍቅር ስላልሆነ ይጨነቃሉ»

በሌላ በኩል ተስፋዬ ገብረአብ በአማርኛ፣ በትግርኛ፣ በኦሮምኛ ወዘተ ... እያሰቡ ዶላርን በእንግሊዝኛ እየቆጠሩ ዝቅተኛ ስራ እየሰሩ በብቸኝነት ስለሚኖሩ ኢትዮጵያውያን አኗኗር ስዕላዊ በሆነ አገላለፅ አቅርቦልናል:: በመጨረሻም ሁሉም ኢትዮጵያ በሀገሩ ሆኖ ስራ ሳይመርጥ ቢሰራ ራሱንም ሆነ ሀገሩን ማሳደግ እንደሚችል ምሳሌ ጠቅሶ ያስረዳናል::

«አሜሪካ ምቹ ናት:: ሆኖም ወርቃማነትዋና ምቹነትዋ የሚገኘው ላብ በማፍሰስ ነው:: አሜሪካ ውስጥ እያንዳንዱዋ ሳንቲም የላብ ውጤት ናት ...»

የቶማስ አርጋውን አሲዳም ዘመን፣ የመስፍን ሀብተማርያምን ፍቅርና ፍቅረኞች፣ የሳሙኤል ተፈራን ሽሙጥ «የብዕር ጥንቅሾች» ብሎ ማለፍ ይቀላል:: ሲሳይ ንጉሱ «እንደገና እንወለድ» ይለናል::

«አስራ ሰባት የወሬ ዓመታት ሲያልፉ ምላስ ከፍተኛውን ቦታ ይዞ ቆይቷል:: ባዶ መፈክር አንግበን፣ ባዶ ጨኸት ስንጮህ፣ ምድሪቷ በድምፃችን ድርቀት ተሰንጥቃ ባድማ ሆናለች:: ምላስ በፈጠነ ቁጥር እግርና እጆች ሽባ እየሆኑ ሄዱ:: ከማምረት ይልቅ ማውራት ተመረጠ:: የሚያሾም፣ የሚያስመርጥ፣ የሚያበላ፣ የሚያጠጣ፣ የሚያኩራ ምላስ ሆኖ ተገኘ ...»

ሲሳይ እንደገና እንወለድ ያለው ከላይ የጠቀስነውን አስነዋሪ ተግባር በመልካም ስነ ምግባር መለወጥ እንዳለብን ለማስገንዘብ ነው::

«... ሽቅብ ወደላይ ብቻ ያንጋጠጠ፣ ዓይናችንንም ወደታች እናሳየው:: ስርቀት ይቅርብን፣ ሰርተን ሀብት እናፍራ፣ ሁላችንም በስራ እንደገና እንወለድ::» (ገፅ 352)

የአቦነህ አሻግሬ «ከአቅም በላይ» በትምህርታዊነቱ፣ የወሰን ይሄይስ «ጌታ ሆይ» በአዝናኝነቱ አድናቆት የሚቸራቸው የጥበብ ውጤቶች ናቸው::

### ሥነ ግጥም

እፍታ ግጥምም አካታለች:: የተስፋዬ ሼክስፒራዊ መወድሶች በእርግጥ ከሼክስፒር የተወሰዱ ይሁኑ አይሁኑ መለየት ባይቻልም፣ (በዚህ ፅሁፍ ሐያሲ) የግጥሞቹ ውበት 'ጣመኝ ድገመኝ' የሚያሰኝ ኪናዊ መአዛ አለው::

የግጥም ነገር ከተነሳ ሳይዳሰስ መታለፍ የሌለበት ነጥብ ግን አለ:: የግጥሞቹ ብዛት ከሚገባው በታች አንሰዋል:: ቢያንስ የአንድ ሶስት ደራስያን የተለያዩ ግጥሞች መቅረብ ነበረባቸው:: በአሁኒቱ እፍታ ግጥም እንደጠማቸው የቀሩ ግጥም አፍቃሪያን በቀጣዩ የሚካሱበት መላ መፈለግ አለበት::

### ካርቱን

የእፍታን ካርቱኖች በሁለት መንገድ ከፍሎ ማየት ይቻላል:: ራሳቸውን ችለው የቀረቡና የድርሰት ገላጭ ሆነው የቀረቡ ወጥ የካርቱን ስራዎች ሙሉ በሙሉ ከሰዓሊው ህሊና የመነጩ የጥበብ ጠብታዎች ናቸው:: ድርሰቶችን አጅበው የቀረቡ ካርቱኖች ደግሞ ሰዓሊው (ለራሱ በሚገባው) ከድርሰቶቹ ይዘት (መልዕክት) በመነሳት ያስቀመጣቸው ናቸው:: እዚህ ላይ የፅሁፍ ደራሲ ለሰዓሊው እንደመሰላል ሆኖ ያገለግለዋል ማለት ነው::

በካርቱን ስዕሎች ላይ ጠለቅ ያለ ሂስ ለማካሄድ በሙያው መካንን ይጠይቃል:: በመሆኑም ዝርዝር ሒሶችን መሰንዘር አይቻልም:: እንደዚያም ሆኖ ግን በእፍታ የቀረቡ የካርቱን ድርሰቶች አያዝናኑ መልዕክት ማስተላለፍ የሚችሉ ብቻ ሳይሆኑ መፅሄቷ ተጨማሪ የስነ ጥበብ ወዝ እንድትላበስ የራሳቸው የሆነ አስተዋፅኦ አበርክተዋል::

### ማጠቃለያ

ፋና ዴሞክራሲ አሳታሚ በእፍታ መፅሀፍ የስራውን እፍታ አቅምሶናል:: ከእፍታ እንደምንረዳው እትምዋ ቀጣይ ትመስላለች:: ይህም መልካም ነው:: ይሁንና አሳታሚው ሁለተኛይቱን የእፍታ ቅፅ ሲያሳትም ሊያጤናቸው የሚገቡ አንድ ሁለት ነጥቦች አሉ::

እፍታ የበርካታ ሥነ ጥበብ ውጤቶች ድምር እንደመሆንዋ መጠን አሁን ከያዘቻቸው በርካታ ቁም ነገሮች በተጨማሪ ምርጥ ጥቅሶች፣ ለሳቅ ለፈገግታ የሚሆኑ አጫጭር ፅሁፎች፣ ቢቻል ምርጥ ፎቶግራፎችና በጥቁርና ነጭ ቀለም የተሳሉ ስዕሎች ብታካትት ይዘታዋ የተሟላ ይሆናል::

ሌላው ነጥብ የዋጋ ጉዳይ ነው:: የእፍታን ዋጋ የተመኑ ወገኖች መፅሀፏን በውስጧ ከያዘቻቸው ቁምነገሮች አኳያ የመዘንዋት ይመስላል:: የወረቀት ዋጋ መናርና የህትመት ዋጋም ጫና ፈጥሮባቸውም ይሆናል:: እንደዚያም ሆኖ በተከታታይነት ለሚወጣ መፅሀፍ ብር 15 (አስራ አምስት ብር) ትንሽ የሚበዛ ይመስላል:: የአንባብያን ቁጥር አነስተኛ በሆነበት ህብረተሰብ ውስጥ የምንኖር ስለሆነ ራስን እየጐዱ ለሥነ ጥበብ «ግብር» መክፈልም ያስፈልጋል:: መልካም ንባብ::

# የጥበብ ስራ

ደራሲ - አንቶን ቼኾቭ
ምጥን ትርጉም - አፈወርቅ ዘለቀ



አንድ ለናቱ የሆነው ሳሻ ስሚርኖቭ በጋዜጣ የተጠቀለለ ነገር በጉያው ሸጉጦ ዶክተር ኮሼልኮቭ ቢሮ ገባ::

«ለመሆኑ እንዴት ነህ? እንደተሻለህ ተስፋ አለኝ» በማለት ዶክተሩ ለሳሻ ሞቅ ያለ አቀባበል አደረገለት፣ ሳሻም ቅንድቡን በማርገብገብ እንደተሻለው ከገለፀ በኋላ በመጣደፍ እጁን ወደብብቱ እየዶለ በስሜት ተናገረ::

«... እናቴ ኢቫን ኒኮላዬቪች ለርሶ ያላትን አክብሮትና ምስጋና እንድገልጽላት ላከችኝ... እኔ ብቸኛ ልጇ ነኝ::.... ህይወቴን አተረፏት:: እርሶን ለማመስገን እናቴም ሆነች እኔ ቃላት ያጥሩናል::»

«ምንም አይደል» ብሎ አቋረጠው ዶክተሩ:: በመቀጠልም «ማንም በኔ ቦታ ቢሆን የሚያደርገውን ነው ያደረግሁት» አለው::

«እኔኮ የእናቴ ብቸኛ ልጇ ነኝ... በርግጥ ድሆች በመሆናችን ለድካምዎ ተመጣጣኝ ዋጋ አልከፈልንም:: በዚህም እማዬና እኔ እፍረት ተሰምቶናል:: ስለዚህ እማዬና እኔ ብቸኛ ልጇ፣ ይህችን አነስተኛ ስጦታ እንዲቀበሉን እንማፀኖታለን:: ከነሐስ የተሰራች ጥንታዊ የወግ ቅርስ ናት፣ እንደልብ የማትገኝ የስነጥበብ ስራ ውጤት!»

«አይገባም» አለ ዶክተሩ ፊቱን በማጨፍገግ::

እባክዎን እንዲህ አይበሉን ዶክተር» አለ ሳሻ ስሚርኖቭ በመማፀን ቅላጼ ጥቅሉን ሙሉ ለሙሉ እየፈታ:: «እንቢታዎ እኔንም ሆነ እናቴን ያሳዝነናል:: ብርቅና ጥንታዊ ቅርስ ናት እኮ፤ የውድ አባቴ ውርስ ናት:: በመታሰቢያነት ነው ያኖርናት:: ነፍሱን ይማረውና አባቴ ቅርሳቅርሶች እየገዛ ለቅርሳቅርስ ሰብሳቢዎች ይሸጥ ነበር:: አሁን ግን የንግዱን ስራ ተረክበን የምናካሂደው እኔና እናቴ ነን::»

ሳሻ ስሚርኖቭ ጥቅሉን ፈቶ በስነስርዓት ዶክተሩ ጠረጴዛ ላይ አኖረው:: አነስ ያለች ከነሀስ የተሰራች ጥንታዊ የሻማ መያዣ ዕቃ ናት::

«...ሆሆይ! ይህን ዕቃ እቤቴ ውስጥ ያየ ምን ይለኛል?»»

የቅርጹ ይዘት ትዝብት ላይ የሚጥል መስመላቸውን (እርቃናቸውን) ያሉ የሁለት ሴቶች ምስል ነው:: ምስሉ ላይ ያሉት ሴቶች ለወሲብ የሚያማልል ቅንዝራዊ ፈገግታ እያሳዩ ከቆሙበት ዘለው ለመውረድና ለአንባቢ ለመግለጽ በሚያስቸግር ሁኔታ በሞቅታ በመድረኩ ላይ ለመውረግረግ ያቆበቆቡ ሴሰኞችን ይመስላሉ::

«ምንም የጥበብ ስራ ቢሆን ከቤቴ ላኖረው አይገባም:: ነውር ነው:: ከነውርነቱም ይህን ምንነቱ የማይለይ ምናባዊ ቁስ ቤቴ ውስጥ ማኖር የቤቴን ውስጥ ውበት ማመሰቃቀል ነው» አለ ዶክተሩ::

«ምን ማለቶ ነው ዶክተር?! ስለስነጥበብ ያሎት አመለካከት ግራ ነውሳ» አለ ሳሻ መከፋቱን በሚገልጽ ድምጽ በመቀጠል በማባበል ዓይነት «እስቲ ያስተውሉት ውበቱ መንፈሶን በሀሴት ይሞላዋል:: ይህን የመሰለ ውበት ሲያስተውሉ አላፊ ጠፊውን ጊዜያዊውን ነገር ጨርሶ ይረሳሉ:: ኧረ በፈጠሮት እስቲ ያስተውሉት::»

«ስለምትለው ነገር ሁሉ በደንብ ተረድቻለሁ ልጄ» በማለት አቋረጡት ዶክተሩ:: ቀጥለውም «ግን እኮ የቤተሰብ ኃላፊ ነኝ:: ህፃናት አሉኝ ወይዛዝርትም ሊጐበኙኝ ይመጣሉ::»

«በርግጥ ከተራው ሰው አመለካከት አንፃር ይህ ብርቅና ድንቅ የጥበብ ስራ ባልሆነ መልኩ ሊተረጐም ይችል ይሆናል:: ግን ዶክተር እስቲ ራሶን ከተራው ሰው መሀል ቀና አርገው ጥበቡን አስተውሉት፣ በተለይ እምቢታዎ እኔና እማዬን ሊያሳዝነን ስለሚችል... ደሞኮ ለእናቴ ብቸኛ ልጇ ነኝ:: ህይወቴን አትርፈዋታል፣ በስጦታ ያበረከትንሎት አለን የምንለውን ምርጥ የወግ ዕቃ ነው፤ ዕቃው ጥንድ ነበር:: ያለን ግን አንዱ ክፋይ ብቻ በመሆኑ ይቅርታ እጠይቃለሁ::»

«አመሰግናለሁ ልጄ:: ለናትህም ያክብሮት ሰላምታዬን አድርስልኝ ግን በፈጠረህ እስቲ እራስህ እየው:: ህፃናት

ያሉበት ቤት ነው:: ወይዛዝርትም ሊጠይቁን ይመጣሉ... ይሁን በጀ ይቆይ ዳሩ አልተረዳኸኝ» አለ በሳሻ ሙዝዝ ማለት ተስፋ የቆረጠው ዶክተር::

«ምንም የምረዳው ነገር የለም» አለ ሳሻ በዶክተሩ እጅ መስጠት በመደሰት:: «ወይ ነዶ! የአጣማጁ አለመኖር እንጂ የበለጠ ድንቅ ስጦታ በሆነ» አለ ሳሻ ተሰናብቶ ሲወጣ::

ሳሻ ከሄደ በኋላ ዶክተሩ የሻማ ማስቀመጫዋን ሲያስተውል ቆይቶ «ውድ ዕቃ ለመሆኑ ጥርጥር የለውም:: መጣልም ተገቢ አይደለም:: እቤቴ ላኖረው ደግሞ አይገባም ... ምን አይነት ዕዳ ነው ጃል? ለማን አባቴ ሰጥቼው እንደምገላገል ነው የጨነቀኝ»

ከብዙ ማሰላሰል በኋላ ጓደኛው ኢኮብ ጠበቃው ትዝ አለው:: የሆነ ጉዳይ በመፈፀም ባለውለታው ነው:: (ምርጥ ሀሳብ) አለ ዶክተሩ:: እንደጓደኛነቱ ለውለታው ገንዘብ አይቀበለኝም:: ያችን የሰይጣን ቁራጭ የመሰለች የሻማ መያዣ በስጦታ በማበርከት ውለታውን አጣጣለሁ::

አላመነታም:: ኮቱን ደርቦ የሳሻን ገፀ በረከት በተራው ሊያበረክት ወደ ጠበቃው ገሰገሰ «ጤና ይስጥልኝ ሽሜው፣ ልጠይቅህ መጣሁ፤ ላረክልኝ ሁሉ ምስጋናዬ ይድረስህ:: ለውለታህ ገንዘብ አትቀበለኝ ይሆናል ብዬ በመስጋት ይህችን አነስተኛ፣ ግን ግርማ ሞገስ ያላት ውድ ስጦታ ላበረክትልህ ወደድኩ:: ምርጥ የስነ ጥበብ ስራ ናት::»

ጠበቃው የሻማ ማስቀመጫዋን በአትኩሮት ሲመለከታት ከቆየ በኋላ ሳቁን ለቀቀው::

«የምን ቁራጭ አመጣህብኝ ጃል? ይህን ሲሰሩ ምን አስበው እንደሰሩት የሚያውቀው ሰይጣን ብቻ ነው» አለ ኢኮብ ጠበቃው ስጦታውን በማጣጣል:: በመቀጠልም የዶክተሩን አፀፋ በመስጋት በር በሩን እያየ «ወዳጄ ስጦታህን ላንተው አርገው::: አልፈልገውም» አለው::

«ለምን ባክህ?» ሲል ዶክተሩ በመጨነቅ ጠበቃ ወዳጁን ጠየቀው:: «ለምን ካልከኝ ጥሩ:: እናቴም እየተመላለሰች ትጠይቀኛለች:: ደንበኞቼም አሉ:: እናም ከዚህ ዕቃህ ጋር አብሬ መታየትን አልሻም::»

«...ስጦታዬን መናቅማ የማይታሰብ ነው» በማለት ጮኸ ዶክተሩ::» በመቀጠልም «ይህ ከጨዋ የማይጠበቅ ስነምግባር ነው:: የስነ ጥበብ ስራኮ ነው:: ወይስ እኔን ልታስቀይመኝ ሀሳብ አለህ?»

ቅርጹን ሲሰሩ ሸፈን ቢያረጓቸው ምን ነበረበት? ሀፍረታቸው ላይ የቅጠል ቅርጽ እንኳን ቢቀርጹባቸው ምንኛ ጥሩ በነበር» አለ ጠበቃው ዕቃውን በትዝብት እያየ::

ዶክተሩ የጠላውን የስጦታ ሸክም በማራገፉ በመደሰት ውልቅ አለ:: ጠበቃው ኢኮብ ከስጦታው ጋር ብቻውን ቀርቷል:: ስጦታውን እያገላበጠ በመፈተሽ ምን እንደሚያደርጋት ሲያሰላስል ቆየ:: ቆንጆዬ ነገር ናት:: አውጥቶ መጣል ነውር ይሆንብኛል፣ ከኔ ጋር ማኖሩም የማይታሰብ ነው:: ያለኝ አማራጭ ለሰው በስጦታ መስጠት ብቻ ነው:: እንዲያውም በዛሬው ምሽት ወስጄ ለኮሚኩ ሻሽኪን እሰጠዋለሁ::: ቧልተኛና እንዲህ ያሉ ነገሮችን የሚወድ ሰው ነው::

እቅዱ ተግባራዊ ሆነ:: የሻማ መያዣዋ ነሀስ በጥንቃቄ ተጠቅልላ ለኮሚኩ ሻሽኪን በስጦታ ተበረከተች::

ምሽቱን የኮሚኩ መልበሻ ስጦታውን ለማየት በመጡ ሰዎች ተጨናነቀች:: ክፍሏ በመገረም ድምጽና እንደ ፈረስ በሚያሽካኩ ሳቆች ተወጥራለች:: ከተዋንያኖቹ አንዷ ወደ መልበሻው ለመግባት ብትጠይቀው (የለም ልብሴን ገና አለበስኩም) ነበር የሚሆነው ምላሹ::

ከትርዒቱ በኋላ ኮሚኩ ሻሽኪን ተስፋ በመቁረጥ ትከሻውን ከፍ ዝቅ አደረገ:: 'ውሎዬ ከጨዋ ቤተሰብ ጋር ነው፤ ወይዛዝርቱን ነው የማዝናናው:: ታዲያ ከዚህ አስቀያሚ ዕቃ ጋር መታየት ከግምት ላይ አይጥለኝም? እኮ የት አባቴ ላርገው? ፍቶግራፍ አይደል አንዱ መሳቢያ ውስጥ አልሸጉጠው...'

«ግን እኮ ሊሸጡት ይችላሉ ጌታው» ሲል ፀጉር አስተካካዩ ምክሩን ለኮሚኩ ሻሽኪን ለገሰው:: «በመቀጠልም በዚሁ አቅራቢያ ጥናታዊ የነሀስ ቅርሶች የምትገዛ አሮጊት አለች:: ስሚርኖቫ ብለው ቢጠይቁ ቤቷን ማንም ያሳዩታል::»

ኮሚኩ ሻሽኪን የፀጉር አስተካካዩን ምክር ተግባራዊ አደረገ::

ከጥቂት ቀናት በኋላ ዶክተር ኮሼልኮቭ በስራ ክፍላቸው ሆነው ስለ ሀሞት አሲድ በተመስጦ እየተመራመሩ ሳለ በሩ በድንገት ተከፍቶ ሳሻ ስሚርኖቭ በደስታ እየተፍነከነከ ዘው አለ:: ፊቱ በደስታ ያበራል:: በእጁ በጋዜጣ የተጠቀለለ ነገር ይዟል::

«ዶክተር» አለ ሳሻ በደስታ ቁና ቁና እየተነፈሰ «የደስታዬን መጠን ይገምቱት፣ እድለኛ ነዎት:: እንዲህ ነው እንጂ ሲያገጣጥም:: እርሶም ደስ ይበሎት:: የበቀደሟን ሻማ መያዣ ነሀስ አጣማጅ (ቀሪ አካል) አገኘንልዎ:: እማዬ እንዴት ተደሰተች መሰሎት::...እኔኮ ለእናቴ አንድ ልጇ ነኝ:: ህይወቴን አተረፏት...»

ሳሻ ስሚርኖቭ ዲስኩሩን አቁሞ በእርካታ ያመጣውን የሻማ መያዣ እዶክተሩ ፊት ከጠረጴዛው ላይ አኖረው::

ዶክተር ኮሼልኮቭ አንዳች ነገር ለመናገር እንደፈለጉ ሁሉ አፋቸውን ከፈቱ ምንም አይነት ድምጽ ማሰማት ግን አልቻሉም:: ምላሳቸው አፋቸው ውስጥ ተሸመደመደች:: □

# እርጅናን ለመከላከል

(ስዩ ስሰን)

እርጅና ሀብትም ጸጋም ነው፤ አስቸጋሪውን የሕይወት ውጣ ውረድ በማቸነፍ፣ የተለያዩ የበሽታ ወጥመዶችን በማለፍ፤ ጥቂት የታደሉ እድሜ ጠገቦች የሚያገኙት የመጨረሻው የሕይወት ማዕረግ በመሆኑ በእርግጥ እርጅና በረከትም ጭምር ነው::

እርጅናን በዚህ ገጽታው በደስታ ተቀብለው የሚያስተናግዱት የመኖራቸውን ያህል በአንጻሩ እርጅናን የሕይወት ፍጻሜ መግቢያ በር ከፋች፣ የሞት አዋጅ ነጋሪ አድርገው የሚያስቡት ደግሞ ገና ከሩቅ ይፈሩታል፤ ይሸሹታል፤ ሸሽተው ባያመልጡም:: በእርግጥ ዕድሜ አይጠገብም፤ ሕይወት በእጅጉ ታጓጓለች፤ ዳግም ስለማናገኛት ይሆን?

ድሮ ነው አሉ፣ ነጋ ጠባ፣ መሸ ነጋ ፈጣሪያቸውን «ዕድሜ ስጠኝ» እያሉ የሚጸልዩ አንዲት ባልቴት ነበሩ:: ከእለታት አንድ ቀን እግዚአብሔር ጸሎታቸውን ሰምቶ በሰው አምሳል ተገለጸላቸውና «ሁል ጊዜ እድሜ ስጠኝ፣ እድሜ ስጠኝ ትያለሽ፤ ለመሆኑ እድሜሽን ምን ያህል እንዳደርግልሽ ትፈልጊያለሽ?» አላቸው:: ሁኔታው ያላሰቡት ያልገመቱት ቢሆንባቸው ጊዜ ደንግጠው ዝም አሉ፤ መልአኩም ደገመና «የፈለግሽውን ያህል እድሜ እጨምርልሻለሁ ተናገሪ» በማለት የእድሜያቸውን ጣሪያ ራሳቸው እንዲወስኑ ፈቀደላቸው::

በዚህን ጊዜ ባልቴቲቱ ይበልጥኑ ተጨነቁ:: አምስት መቶ ሌሊት ፈለጉና ሲያስቡት አነሰባቸው፤ አንድ ሺህ... ሁለት ሺህ... አምስት ሺህ... አስር ሺህ... ሁሉም አላረካቸውም:: አንድ ሚሊዮን ቢሉ እንኳን አንድ ቀን መሞታቸው እንደማይቀር ታሰባቸው:: በዚህን ጊዜ «ምናለ አንድ እኔን ብትተወኝ» አሉትና አረፉት::

ነገሩ በእርግጥ የተፈጸመ ድርጊት ወይም ያልተደረገ «ተረት» ሊሆን ይችላል:: አንድ ነገር ግን እውነት ነው:: ሞት አይቀርም፤ የሰው ልጅም ዕድሜ በቃኝን አያውቅም::



ወደዋናው ርእሳችን እንመለስ ወደ እርጅና የተፈጥሮ ክስተት ቢሆንም አንዳንዴ ከተመደበለት የእድሜ ክልል ፈጥኖ በመምጣት የጉልማሳነትን ዘመን ሊሻማ ይችላል:: እርስዎስ ያለ እድሜያቸው ካረጁ አንዱ ነዎት? ብዙም አይጨነቁ፤

የፊትዎ ቆዳ ሊጨማደድ ፣ ጸጉርዎ ሊሸብት፣ ይችላል:: አቅምና ጉልበትም ሊክድዎት ዳር ዳር ሊሉ ይችላሉ:: እጅዎን አይስጡ፤ እርጅናን እስከነአካቴው ማስቀረት ባይቻልም መከላከል ግን ይቻላል:: ቀጥሎ የተዘረዘሩትን ስድስት መመሪያች እየተከታተሉ በተግባር ላይ ያውሉ:: ከስድስት ሳምንታት በኋላ ከዛሬ አስር ዓመታት በፊት የነበረዎትን መልክና የሰውነት አቋም መልሰው ያገኙታል::

## 1. በአመጋገብ ሰውነትን ማደስ

እርጅናን ከምንከላከልባቸው ዘዴዎች ቀዳሚው አመጋገብን ማስተካከል ነው:: እርጅናን ከሚከላከሉ የምግብ ዓይነቶች አንዱ ዓሣ ነው:: ከዓሣም ደግሞ «ዓሣ» አለ:: በውስጡ ኦሜጋ - 3 የተሰኘውን ንጥረ ቅመም በብዛት ያለበት ቢሆን ይመረጣል:: ሳልሞን ሰርዲን ከተገኘም መልካም ነው::

የዓሣ ስጋ ለልብ ጤንነት ፍቱን ነው:: ልብ ደግሞ የሰውነታችን ሞተር ነው:: የዓሣ ስጋ ግን በልብ ብቻ ተወስኖ የሚቀር አይደለም:: ለአእምሮአችን ጤንነትም በእጅጉ ጠቃሚ ነው:: በካሊፎርኒያና በሎስአንጀለስ ዩኒቨርስቲዎች በተደረጉ ጥናቶች ዓሣን አዘውትረው የሚመገቡ ሰዎች በካንሰር (ነቀርሳ) የመያዝ እድላቸው አነስተኛ ሆኖ ተገኝቷል:: የዓሣ ስጋ በተለይ የጡት ካንሰርን በመከላከል የጉላ ሚና እንዳለውም ጥናቶች ያረጋግጣሉ::

አረንጓዴ ተክሎችና ፍራፍሬዎችም እርጅናን በመከላከል በኩል ትልቅ ሚና ይጫወታሉ:: በሜይታን ዩኒቨርስቲ የምግብ ሳይንስ መምህርት የሆኑት ሜሪ ኤለን እንደ ሚሉት በየቀኑ የተወሰኑ ፍራፍሬዎችና አትክልቶችን መመገብ ለጤንነት ዋስትና ነው::

## 2. ተፈጥሮአዊ ሕክምና መጠቀም

ብዙ ሰዎች (በተለይ ሴቶች) ፊታቸው የመጨማደድ ምልክት ሲያሳይ በኤሌክትሪክ የሚሰራ «ፊት አለስላሽ» የፊዝዮትራፒ ሕክምናን ይጠቀማሉ:: የዚህ ዓይነቱ ሕክምና በተወሰነ ደረጃ ሊሰራ ይችል ይሆናል::

ዘላቂነት ግን የለውም::

ከሁሉ የሚሻለው ባሕላዊው የአኩፓንክቸር (የደረቅ መርፌ) ሕክምና ነው:: ጆን ማይርሰን የተባሉ አኩፓንክቸሪስት ደረቅ መርፌ ከማንኛውም ዘዴ በላይ በፊታችን ላይ የሚከሰት የቆዳ መሸብሸብን በማስወገድ ለስላሳና ደመ-ግቡ ፊት እንዲኖረን ያደርጋል:: የዚህ ምስጢር ደረቅ መርፌ በፊታችን ላይ የተዘረጉትን እልፍ አእላፍ የደም ስሮችን በማነቃቃት በውስጣቸው ደም እንደልብ እንዲዘዋወር ስለሚያስችል ነው:: ዛሬ በአሜሪካና በአውሮፃ የ55 ና የ60 ዓመት አሮጊቶች በደረቅ መርፌ ጥበብ አማካኝነት በሳምንት ጊዜ ውስጥ የተጨማደደ ገጽታቸውን ማስወገድ ችለዋል:: በባለሞያ የተደገፈ «የፊት ስፖርትም» ጠቃሚ ነው::

## 3. የአካል ብቃት እንቅስቃሴን ማዘወተር

የአካል ብቃት እንቅስቃሴ ለጤንነት ጠቃሚ መሆኑ ከታወቀ ዘመናትን አስቆጥሯል:: በተለይ የትንፋሽ አካላትን የሚያነቃቁ የአካል እንቅስቃሴዎች ሰዎችን ለብዙ ጊዜ «ወጣት» እንደሆኑ የማቆየት ብቃት እንዳላቸው ተረጋግጧል:: የአካል ብቃት እንቅስቃሴ የአጭር ጊዜና የረዥም ጊዜ ጠቀሜታ አለው:: የአጭር ጊዜ ጠቀሜታው የደም ዝውውርን በማስተካከል ቆዳን ልስላሴና ወዘና እንዲኖረው ማስቻል ሲሆን የረዥ ም ጊዜ ውጤቱ ደግሞ የደምና የመተንፈሻ አካላት ስርዓትን የተስተካከለ እንዲሆን ማድረጉ ነው::

እንደዛም ሆኖ የአካል ብቃት እንቅስቃሴ ሲባል ባለብዙ ዘርፍ ስለሆነ አሁን ለተነሳንበት ነጥብ የሚሆን መምረጥ የግድ ነው:: የስነ አካልና የስፖርት ሳይንስ ጠቢብ የሆኑት ስታን ግራንት (Stan Grant) እንደሚሉት ለሴቱም ለወንዱም በጋራ ጠቃሚ ሆኖ የተገኘው የአካል ብቃት እንቅስቃሴ <u>የእግር ጉዞ ነው</u>::

በመስኩ ጥናትና ምርምር ያካሄዱ ባለሞያዎች አንድ ሰው በሳምንት ቢያንስ አምስት ቀናት የእግር ጉዞ ማድረግ አለበት:: የእግር ጉዞው ጠዋት ጠዋት ቢሆን ይመረጣል:: ማንም ሰው ጠዋት ወደ ስራው ሲሄድ የተወሰነ ርቀት በእግሩ ቢጓዝ መልካም ነው? የእግር ጉዞ መንታ ጥቅም አለው፣ አካላዊ ብቃትን ከማስገኘቱ ባሻገር የመንፈስ ጭንቀትን በማርገብ የላቀ ሚና ይጫወታል:: «ዘ.ኒው ኢንግላንድ ጆርናል ኦቭ ሜዲስን» በቅርቡ ባወጣው አንድ ጽሑፍ በቀን ሁለት ማይልስ ያህል በእግራቸው የሚጓዙ አዛውንቶች እድሜያቸው ከሚጠበቀው በላይ ጨምሮ መገኘቱን መረጃዎችን በማጣቀስ አስፍሯል::

እንግዲህ እርስዎም ከዛሬ ጀምረሁ ልወዝወዘው በእግሬን ያዘወትሩ:: «ልምድ የለኝም፣ እንዴት እችለዋለሁ?» እያሉ ራስዎን አያስጨንቁ:: ሁሉም ቀስ በቀስ ይለመዳል:: ለመጀመሪያው ሳምንት በቀን ለ10 ደቂቃ ያህል ቢጓዙ በቂ ነው:: ቀስ በቀስ ጊዜዎን ወደ 30 ደቂቃ ከፍ ያድርጉት:: በጥቂት ሳምንታት ውስጥ ተጨባጭ ለውጥ ያያሉ::

## 4. የእንቅልፍ ጊዜዎን ማስተካከል

እንቅልፍ ለሰውነታችን የምግብ ያህል አስፈላጊ ነው:: በመሆኑም ለአመጋገባችን ውስን ሰዓት እንዳለን ሁሉ የመኝታ ሰዓታችንም ውስንና በፕሮግራም የተያዘ መሆን አለበት:: በሀገረ እንግሊዝ በተደረገ አንድ ጥናት መሰረት ከስድስት እንግሊዛውያን መካከል አንዱ ሰላማዊ እንቅልፍ አይተኛም:: ሰላማዊ እንቅልፍ ያላገኘ ሰው ደግሞ በቀን ስራውን በሚገባ ማከናወን ያዳግተዋል፣ ይደክመዋል፣ ያንጉላጀዋል፣ እንቅልፍ እንቅልፍ ይለዋል፤ ወዘተ

ለዚህ ሁሉ መድኃኒቱ የተስተካከለና ቋሚ የሆነ የእንቅልፍ ፕሮግራም ማበጀት ነው:: የሚተኙበት ሰዓት ውስን መሆን አለበት፣ በሌላ አገላለጽ ዛሬ በሶስት፣ ነገ በአራት ሰዓት ባይሆን ይመረጣል::

በሌላ በኩል ለሰላማዊ እንቅልፍ እንቅፋት ሊሆን ከሚችሉ እንደ ቡና ያሉ ካፊ የበዛባቸው መጠጦች፣ አልኮል፣ ሲጋራ ራስዎን ማግለል አለብዎት:: እነዚህን ነገሮች መተው ካልቻሉ ቢያንስ ከመተኛዎ አራት ሰዓት በፊት ከእነዚህ አንዱንም መውሰድ የለብዎትም::

«አንድ መለኪያ ወይን ወይም አንድ ሁለት ብርጭቆ ቢራ ብጎነጭ ለእንቅልፍ ይረዳኛል!» ብለሁ ያስቡ ይሆናል:: የአልኮል መጠጥ ሲወስዱ ለመጀመሪያ ቶሎ እንቅልፍ ሊያሸልብዎት ይችላል:: ዘላቂና ሰላማዊ እንቅልፍ እንዲያገኙ ግን አይረዳዎትም::

## 5. ቆዳን መንከባከብ

ማርጀትዎን ከሚያጋልጥብዎ አንዱ የፊትዎ ቆዳ መለወጥ (መጨማደድ፣ መጥቆር፣ አመድ መምሰል) ነው:: ቆዳችን የሚጎዳው ውጫዊ በሆኑ ኃይሎች ብቻ አይደለም፤ ለምሳሌ ብዙዎቻችን ሲጋራ ሳንባችንን ብቻ የሚጎዳ ሊመስለን ይችላል፣ ግን አይደለም:: አንጀታችንንም አእምሮአችንንም ያቆስላል:: ሲጋራ በውስጡ የቋጠራቸው ከ100 በላይ መርዛማ ንጥረ ቅመሞች ሌላም ጣጣ አላቸው:: ሲጋራ የሰውነታችን ቆዳ እንዲደርቅ ተሎ እንዲኮማተርና እንዲጨማደድ ሁኔታዎችን ያፋጥናል::

ሰው ሰራሽ ቅባቶች የተጨማደደን ቆዳ በማለስለስ በኩል እገዛ ሊያደርጉ ቢችሉም መሰረታዊው መፍትሔ ግን ከሲጋራ ከአልኮልና ከሃይለኛ የፀሐይ ጨረር ራስን ማራቅ ነው::

## 6. ጠንካራ ሰውነት መገንባት

ነገሩ ከአካል ብቃት እንቅስቃሴ ጋር የተዛመደ ቢሆንም ልዩነት አለው:: አንድ ሰው እድሜው ከ40 በላይ ሲሆነው በአንድ ዓመት ውስጥ በሰውነቱ ውስጥ ካሉት ጡንቻዎች ሲሶው ያህል ይሞታሉ:: በሌላ አገላለጽ እያረጀ ነው ማለት ነው:: ለዚህ መከላከያ መድኃኒቱ ጡንቻን የሚያጠናክሩ የአካል እንቅስቃሴዎችን ማዘወተር ነው:: የዚህ ዓይነቱ እንቅስቃሴ ግን በዘፈቀደ የሚደረግ አይደለም:: የባለሞያ ምክርና እገዛ ያስፈልጋል:: በነገራችን ላይ ከአጠቃላይ ሰውነታችን ውስጥ 40% ጡንቻ መሆኑን ያውቃሉ?

**ምንጭ**

ፊደርስ ዳይጀስት ግንቦት 1998 እ.ኤ.አ



# የጨለማ ጉድጓዶች

የህዋ ቢርሙዳ ትሪያንግል?

... ከተፈጥሮ ህግጋት ያፈነገጡ፣ ከፍጡራን እይታ ውጪ ያደፈጡ፣ እጥጋቸው የደረሰን ካለምንም እፍታ ጨፍልቀው ወደ ምንምነት የሚለውጡ... ስግብግብ፣ ድራሽቢስ የህዋ አውሬዎች... የጨለማ ጉድጓዶች!

አስተሮ- ፊዚስት ቻንድራ ሲካር ሆስፒታል የገቡበት ሰሞን የሰለጠነው አለም ስለጨለማ ጉድጓዶች የበለጠ ለማወቅ ያሰፈሰፈበት ሰሞን ነበር:: «ሁሉም ነርስና ዶክተሮች ሊቁን ከበቡዋቸው::» ብሎ የጀመረው የወቅቱ የቺካጉ ዩኒቨርሲቲ ዘገባ «ያ ሁሉ ርብርቦሽ ግን የዕውቁን ሳይንቲስት ህይወት ለማትረፍ አልነበረም፣ ስለ ጨለማ ጉድጓዶች ምንነት ከባለሙያው አንደበት ለመስማት እንጂ» በማለት ነበር የዜናውን ታላቅነት በምሳሌ የገለጸው::



«ሙያዬን ስናገር ደብሮዋቸው ማዛጋት የሚጀምሩ ሁሉ ስለ ጨለማ ጉድጓዶች እንደማጠና ፍንጭ ከሰጠኋቸው ሁለመናቸው ጆሮ ይሆናል» በማለት ነበር አንድ ወጣት አስትሮኖመር ዜናው የፈጠረውን ስሜት ለመግለጽ የሞከረው::

የኛው ጋላክሲ ከሚሊዮን የሚልቅ ብዛት ያላቸው የጨለማ ጉድጓዶች /Black Holes/ እንዳሉት ያውቃሉ?

ለመሆኑ የጨለማ ጉድጓድ ብሎ ነገርስ ምንድነው?

ይህንን ከረጅምና ውስብስብ ሂደት በኋላ የተፈጠረ ሳይንስ- ወለድ ስያሜ ለመመርመር ከ200 ዓመታት በፊት የብርሃንን ተፈጥሮ አስመልክተው ከቀረቡት ሁለት ሳይንሳዊ ንድፈ- ሃሳቦች መንደርደር የግድ ይሆናል::

አንደኛውና ሰር አይዛክ ኒውተን በተባለ የፊዚክስ ሊቅ የተቀመጠው ንድፈ- ሃሳብ የብርሃን ስሪት ከብናኝ ቁስ አካላት /particles/ መሆኑን ሲያትት ሁለተኛው ደግሞ ብርሃን የተሰራው ከብርሃን ሞገዶች/light waves/ ነው የሚል ነበር::

ሳይንስ በዛሬው የእድገት ደረጃው የተቀበለው የሁለቱን ንድፈ- ሃሳቦች ቅይጥ ነው:: ብርሃን የብናኝ ቁስ አካላትና የብርሃን ሞገዶች ስሪት ነው ብለው ነው የሚያምኑት የዛሬዎቹ ሊቃውንት::

የብርሃን ስሪት ከብርሃን ሞገዶች ነው በሚለው አስተሳሰብ ስር ስበት /gravity/ በብርሃን ላይ ስለሚኖረው ተጽእኖ ወይም ብርሃን ለስበት ተጽእኖ ስለሚኖረው ምላሽ ምንም መናገር አይቻልም:: ነገር ግን ብርሃን የብናኝ ቁስ አካላት ስሪት ነው የሚለውን ንድፈ- ሃሳብ ለመቀበል የደፈረ ሁሉ የስበትን ተጽእኖ ባፋ ሙሉ ከመናገር የሚያግደው /የሚያጠራጥረው/ ነገር አይኖርም:: እንደ ኳሶች፣ እንደ ሮኬቶች፣ እንደ ፕላኔቶች... ሁሉ እነዚህ ቁስ አካላትም ለስበት ተጽእኖ እጃቸውን ይሰጣሉ::

የብረሃን ፍጥነት የትዬለሌ /infinite/ በመሆኑ ከስበት ህግ ጋት ውጪ ነው:: ብለው ነበር ቀደምቶቹ ተመራማሪዎች የሚያምኑት:: እናም ገደብ የለሽ በሆነ ፍጥነት የሚጓዙትን ብናኝ ቁስ አካላት በዚህ ፍጥነት ከመጓዝ የሚያለዝባቸው ስበት አይኖርም ለማለት ደፈሩ:: ነገር ግን ሮመር ከተባለ ሊቅ ግኝት ወዲህ የብርሃን ፍጥነት ውሱን /finite/ እንጂ የትዬለሌ አለመሆኑ ሲታወቅ ስበት በብርሃን ላይ ስለሚያሳርፈው ተጽእኖ መናገር የሚያስችል ፍንጭ ተገኘ::

የካምብሪጅ ዩኒቨርሲቲ ፕሮፌሰር የነበረው ጆን ሚሼል /1783 እ.ኤ.አ/ በኢምንት ይዘቱ ባካተተው የቁስ አካል ክምችት ስለተጠቀጠቀ ኮከብ ሲናገር የዚህ ዓይነት ኮከብ ከአካሉ

የሚመነጩ ጨረሮችን ጉትቶ ማስቀረት የሚችል ብርቱ የስበት ሃይል በውስጡ ሊያዳብር ይችላል ብሎ ነበር:: እናም ማንኛውም ከኮከቡ የሚመነጭ ብርሃን ብዙ ከመራቁ በፊት በኮከቡ የስበት ሃይል ተጉትቶ ወደ ተነሳበት ለመመለስ ይገደዳል እንደ ሊቁ አባባል:: ሚሼል እንዲህ ዓይነት በርካታ ሙት ክዋክብት ሊኖሩ እንደሚችሉ ቢጽፍም ብርሃናቸው ለእይታችን የመብቃት እድል ስለማያገኝ መኖራቸውን በአይን ምስክርነት ማረጋገጥ አንችልም ብሎ ነበር:: ዛሬ የዘመናችን ሳይንስ የጨለማ ጉድጓዶች /Black holes/ በሚል ስያሜ የሚጠራቸው ከላይ በግርድፉ የተገለጹትን አካላት ነው::

የጨለማ ጉድጓዶች ከፍጥረት እስከ ህልፈት ያለው የግዙፍ ክዋክብት ተፈጥሮአዊ የለውጥና የቅስቃሴ /Motion/ ሂደት አራት ነጥቦች ናቸው እንደ አልበርት አንስታይን እመነት:: ስለነዚህ ትንግርታዊ አካላት በቂ ግንዛቤ ለማስጨበጥ እጅግ ውስብስብ በሆኑ የስበትና የአጠቃላይ አንፃራዊነት /General relativity/ ንድፈ- ሃሳብ ስሌቶች ውስጥ መዝለቅ ከዚህ ጽሑፍም ሆነ ከጽሑፉ ባለቤት አቅም በላይ ስለሆነ ለአጠቃላይ ግንዛቤ በሚያበቁን ሃሳቦች ዙሪያ ለመሽከርከር እንገደዳለን::

ስለ ጨለማ ጉድጓዶች ምንነት ለመረዳት የከዋክብትን የህይወት ሂደት ቢያንስ በግርድፉ መመልከት የግድ ነው ይላል ሌላው የክፍለ ዘመናችን የንድፈ- ሃሳባዊ ፊዚክስ ሊቅ እንግሊዛዊው ስቴፈን ሆኪንግ:: አንድ ኮከብ ተጸነሰ የምንለው መጠነ ብዙ የጋስ ክምችት /ብዙውን ጊዜ ሐይድሮጅን/ በራሱ የስበት ሃይል ተጽእኖ ስር ሲወድቅ፣ በሌላ አባባል በተወሰነ ክልል ውስጥ ዳመና ሲፈጥር ነው:: ይህ የጋስ ደመና ይዘቱን እየቀነሰ /እየተኮማተረ/ ሲመጣ የጋሱ አተሞች ፍጥነትና እርስ በእርስ የመጋጨት ድግግሞሽ እያየለ ይሄዳል:: በዚህ ውስጣዊ ትርምስ ሳቢያ ሙቀት ይፈጠራል:: ሙቀቱ በከፍተኛ ፍጥነት የሚላተሙት ሃይድሮጅን አተሞች ተጣብቀው እንዲቀሩ ለሚያደርጋቸው ኬሚካላዊ ተቃርኖ ምቹ ሁኔታን ይፈጥራል:: እናም የሚጣበቁት አተሞች ሂለየም የተሰኘውን ጋስ ይፈጥራሉ:: ይህ የሃይድሮጅን ቦምብ ፍንዳታ ቀጥተኛ አምሳል የሆነ ተቃርኖ የሚፈጥረው ብርቱ ሙቀት ለከዋክብት ብርቅርቅታ ምክንያት ይሆናል:: ሙቀቱ ለከዋክብቱ ብርሃን መንስኤ ከመሆኑ ባሻገር ዳብሮ ለቆየው ግፊት መጨመርም አይነተኛው ምክንያት ይሆናል:: ባቅጣጫው የስበቱ ተቃራኒ የሆነው ይህ ግፊት ከስበቱ ኃይል ጋር እስኪመጣጠን ድረስ ያይላል:: ግፊትና ስበት ሲመጣጠኑ ደመናው መኮማተሩን ያቆማል::

አንድ ኮከብ የህይወቱን ከፊል ዑደት አጠናቆ ምሉዕ ኮከብ /Stable Star/ የሚሆነው እዚህ ደረጃ ላይ ሲደርስ ነው:: የአንድ ኮከብ መላ የህይወት ታሪክ የእኒህ ተቃራኒና ተመጣጣኝ ግዙፉ ሃይሎች ፍልሚያ ነው እንደ ሊቃውንቱ አገላለጽ:: - የኮከቡን ጋሶች ወደ ውጪ የሚገፋቸው የኒዮክኒያር ተቃርኖ ውጤት የሆነው ሙቀትና ጨረራ / Radiation/ ባንድ በኩል፣ እነዚህኑ ንጥረ ነገሮች ወደ ኮከቡ እምብርት የሚጉትታቸው ስበት በሌላ በኩል::

ፀሀይ ብለን የምንጠራት የኛይቱ ኮከብ የስበቷን ተጽእኖ ለአምስት ቢሊዮን አመታት ለመቋቋም የሚያስችል ነዳጅ እንዳላት ይናገራሉ ሊቃውንቱ:: በሌላ አባባል ይህቺ ኮከብ ለሌላ አምስት ቢሊዮን አመታት ምሉዕ ኮከብ ሆና ትቆያለች ማለት ነው::

ነገር ግን ከፍጥረት የጀመረው ተፈጥሮአዊ ኡደት እስከ ህልፈት ይቀጥል ዘንድ የግድ ነውና ከጊዜ ወደ ጊዜ ሃይድሮጅንና ሌሎችም የሙቀት ምንጭ የሆኑ ኒዮክሊያር ነዳጆች ቀስ በቀስ እየተገባደዱ ይመጣሉ:: ግዙፍ ክዋክብት ግዙፉን ስበታቸውን ለመቋቋም በርካታ ነዳጅ ያባክናሉ:: ይህ ብክነት ለከዋክብቱ ሁለንተናዊ ቅዝቃዜና መኮማተር ምክንያት ይሆናል::

እንደ ፖውሊ ኤክስክሉዥን ንድፈ ሃሳብ ከሆነ በኮከቡ የመኮማተር ሂደት ሳቢያ የሚጨናነቁት ብናኝ ቁስ አካላት /Particles/ ከዚያ በላይ መተፋፍግ /መጠጋጋት/ ከማይችሉበት የመጨረሻ ደረጃ ላይ ስለሚደርሱ የኮከቡ ራዲየስ የማይለወጥ /ቋሚ/ ይሆናል::

ነገር ግን ቻንድራ ሴካር የተባለው አስትሮ ፊዚስት /1928 እ.ኤ.አ/ ይህ ንድፈ ሃሳብ ትክክል የሚሆነው ኮከቡ መኮማተር ከመጀመሩ በፊት የያዘው ቁስ አካል ክምችት /Mass/ ከፀሐይ 2/3 የቁስ አካል ክምችት ያነሰ እስከሆነ ብቻ ነው የሚል ገደብ አስቀመጠ:: ይህ ገደብ የቻንድራ ገደብ የሚል ስያሜ ተሰጠው::

እናም ከቻንድራ ገደብ በታች የቁስ አካል ክምችት ያለው ኮከብ ከተወሰነ መጠን በታች ሊኮማተር አይችልም:: እዚህ ደረጃ ላይ የደረሰ ኮከብ ድንክዬ ኮከብ ይባላል በስነ- ፈለክ /Astronomy/ ሊቃውንት አጠራር:: ኮከቡ የማይለወጥ ይዘት /ቋሚ ራዲየስ/ የሚኖረው በመካከላቸው በነበረው በቂ ርቀት ሳቢያ ተቻችለው የቆዩት የብናኝ ቁስ አካላቱ ኤሌክትሮኖች ከመተፋፈግ

/መጠጋጋት/ በኋላ ስለሚገፋፉ ነው::

ላንዳው የተባለው ሌላው የፊዚክስ ሊቅ ደግሞ በውስጣቸው የፀሃይን ያህል ወይም እጥፍ የቁስ አካላት ክምችት የያዙ ነገር ግን ከድንክዬ ከዋክብት ያነሱ ሌሎች ከዋክብት መኖራቸውን ጠቆመ:: እነዚህኞቹ የማይለወጥ መጠን /ቋሚ ሬዲየስ/ የሚኖራቸው እንደ ድንክዬዎቹ በተፋፈጉ ኤሌክትሮኖቻቸው መገፋፋት ምክንያት ሳይሆን በብናኝ ቁስ አካላቱ ኒውትሮኖችና በፕሮቶኖቻቸው መካከል በሚፈጠረው መገፋፋት ሳቢያ ነው:: በዚህ ምክንያት እኒህ ከዋክብት የኒውትሮን ከዋክብት የሚል ስያሜ ተሰጣቸው::

እንግዲህ ሳይንስ «ኋይት ዱዋርፍ» እና «የኒውትሮን ከዋክብት» ብሎ የሚጠራቸው በዚህ የመኮማተር ሂደት ውስጥ ዘልቀው ከማይለወጥ የመጨረሻ መጠን ላይ የደረሱ አካላትን መሆኑ ነው::

የአንስታይንን ስሌት የተቀበሉ ሊቃውንት የኒዮክሊያር ነዳጃቸውን አገባደው መሬትን እስኪያክሉ ተኮማትረው ድንክዬ ስለሚሆኑት ኋይት ዲዋርፎች ሲናገሩ ከኒህ አካላት ላይ የሚወሰድ አንድ ኪዮቢክ ሴንቲ ሜትር የቁስ አካል ክምችት እስከ አንድ ቶን ሊመዝን ይችላል ይላሉ::

የኒውትሮን ከዋክብት ሬዲየስ እስከ 10 ማይል ሊያንስ የሚችል ሲሆን አንድ ኪዮቢክ ሴንቲሜትር የቁስ አካል ቁንጣሬያቸው ከመቶ ሚሊዮን ቶን በላይ ይከብዳል::

ለአምስት ቢሊዮን አመታት ምሉዕ ኮከብ ሆና እንደኖረችና ለተጨማሪ አምስት ቢሊዮን አመታት የስበቷን ተጽእኖ ተቋቁማ /ምሉዕ ሆና/ እንደምትቆይ የተነገረላት የኛይቱ ፀሐይ ነዳጇን ስታገባድድ ድንክዬ ኮከብ የመሆን እጣ ይጠብቃታል:: እምብርቷ ውስጥ ያለውን አብዛኛውን ኃይድሮጅን አቃጥላ ከጨረሰች በኋላ የአካባቢዋን ኃይድሮጅን ማጋየት ስትጀምር የጋለ የብረት አለሎ መስላ ታብጣለች:: እዚህ ደረጃ ላይ የደረሰች ጊዜ ሜርኩሪ፣ ቬነስና የኛይቱ መሬት በሚፋጅ የጋለ ነፋሪት ይመታሉ::

ግዙፍ ከዋክብት ነዳጃቸውን ባገባደዱ መጠን ከተቃራኒው ኃይል እያየለ ሲገዝፍ በቆየ ስበታቸው ለመኮማተር ይገደዳሉ:: አካላቸው የገዛ ስበታቸውን መቋቋም ከማይችልበት ደረጃ ላይ የደረሱ ጊዜ ግን ሁለንተናቸውን ሲጨምቀው የቆየው የትዬለሌ ስበት ብቻ ይቀርና ከዋክብቱ ከነግሳንግሳቸው በገዛ ከርሳቸው ውስጥ ይከስማሉ::

ጀርመናዊው ሳይንቲስት ካርል ሽዋዝቻይልድ በ1955 የአንስታይን የአንፃራዊነት ንድፈ- ሃሳብ ለሳይንሱ አለም ይፋ በሆነበት ሰሞን በዚሁ ንድፈሃሳብ ላይ የተመረኮዘ አስተያየቱን ሲሰነዝር- የትዬለሌው ስበት ሙቁን ኮከብ በጊዜና በቦታ ተከትቦ በገዛ ከርሱ ውስጥ እንዲከስም ያደርገዋል ብሎ ነበር::

የፀሐይን ያህል የቁስ አካል ክምችት ያለው ኮከብ የገዛ ስበቱን መቋቋም ከማይችልበት የመጨረሻ ነጥብ ላይ የሚደርሰው ሬዲየሱ 3 ኪ.ሜ /2 ማይል/ እስኪሆን ድረስ ከተኮማተረ በኋላ ነው:: ከዚህ ሬዲየስ በታች የሚኮማተር ኮከብ ከናካቴው ወደ ምንምነት ይጨፈለቃል:: /እንዳልነበር ይሆናል/ ይህ የመጨረሻ ሬዲየስ የሽዋዝቻይልድ ሬዲየስ ተብሎ ይጠራል:: ሬዲየሱ በእኒህ በገዛ ስበታቸው ድራሻቸው በጠፋ ትንግርቶች ተጽእኖ ስር ያለውን አድማስ የሚያካልል ሲሆን ሳይንስ ይሄንን አድማስ ኢቨንትሆራይዘን ብሎ ይጠራዋል:: ኢቨንት ሆራይዘን እድሜ አለማቸውን ከዚያ መአተኛ ከርስ ለማምለጥ የሚቃጡ የብርሃን ልቃቂቶች በየትዬለሌው ስበት ታንቀው እስኪመለሱ ድረስ የሚዳስሱትን የመጨረሻ ርቀት ያካልላል::

እናም የጨለማ ጉድጓድ የተሰኘው ሳይንስ ወለድ ስያሜ የዚህ ከፍጡራን እይታ ውጪ የሆነ ከርሰ ስያሜ ነው::

ብርሃን ማምለጥ ካልቻለበት ከርሰ ከቶ ምንም ነገር ሊያመልጥ አይችልም:: ወደ ጨለማው ጉድጓድ አድማስ የተጠጋ ሁሉ ካለ ምንም ቆይታ ተጨፍልቆ ውጦ ቁልጭ ከሆነው ከርስ ውስጥ ይገባና ይከስማል:: ራሳቸውን ወደ ምንምነት በጨፈለቁ እና የተጠጋቸው ወደ ምንምነት ለመጨፍለቅ ባሰፈሰፉት በኒህ የህዋ አዚሞች አድማስ ውስጥ ጊዜና ቦታ ከቶም ትርጉም የላቸውም:: ያለማችን ታላቅ ትንግርት ያደረጋቸውን የትዬለሌ ስበትና ለመኖራቸው ቅንጣት ምልክት የማይታይበትን ድራሻቸውን ያካተተው አድማሳቸው ጊዜንና ቦታን አያውቃቸውም:: ለዚህ ነው ካለ ምንም ቆይታና ወደ ምንምነት የሚለውን ቅጥ የለሽ አባባል ለመጠቀም የምንገደደው::

የአንስታይንን ንድፈ- ሃሳብ ትክክለኝነት ለተቀበለ ህሊና የጨለማ ጉድጓዶች የህይወት ኡደታቸውን ያጠናቀቁ ሙት ከዋክብት ናቸው:: እናም ቁስ አካሉ በገዛ ስበቱ ተጨምቆ ከምድረ ገጽ ጠፋ ማለት የሂሳብ ሊቃውንት ሲንጉላሪቲ ብለው የሚጠሩትን ጊዜና ቦታ የማይታወቁበትን ዓለም ሆኖአል ማለት ነው::

ሺፈራው ከበደ

□



# ዡሌስ ቨርን ባለራዕይ ደራሲ

(ከእኑዬ)

ጊዜው በ1800ዎቹ ውስጥ ነው፤ ከእለታት አንድ ቀን አንድ ባለቀይ ሪዝ ሰው ፈረንሳይ ትምህርት ሚኒስቴር ቢሮ ገብቶ ማንነቱን የምታሳየውን ካርድ ለእንግዳ ተቀባዩ ግለሰብ ሰጠ። ተቀባዩ ካርዷን እንዳየ ፊቱ በፈገግታ አበራ። ወዲያው «የተከበሩ ቨርን ባደረጉት ረዥም ጉዞ ሳይደክምዎት አልቀረምና አረፍ ይበሉ» ብሎ በአክብሮት የሚቀመጥበትን ወንበር አቀረበለት። በእርግጥም ታላቁ የብዕር ሰው በጣም ሳይደክመው አልቀረም፤ አይፈረድበትም፤ ቨርን አንድ ቀንም አርፎ አያውቅም፤ ሁሌም ዓለምን ይዞራል፤ ቢያንስ በ80 ቀናት ውስጥ አንዴ ዓለምን ያዳርሳታል። ሌላው ቢቀር በ69 ሺ ኪሎ ሜትሮች ያህል በጥልቅ ባህሮችና ውቅያኖሶች ውስጥ ተጉዟል። ጨረቃ ድረስም ዘልቋል፤ የመሬትን እምብርት (ውስጣዊ አካል) ሳይቀር አስሷል። አፍሪቃ መሀል ድረስ በመጓዝ በላኤ ሰዎች ጋር ተዋውቋል። አትላንቲክን በማቋረጥ ከአሜሪካ ኦሪኖኮ ህንዶች ጋርም. ተወያይቷል። ባጭሩ ደራሲው ዡሌስ ቨርን ያልጎበኘው የዓለም ክፍል ቢኖር በጣም ትንሽ ነው። እንደዚያም ሆኖ ዡሌስ ቨርን ከቤቱ ወጥቶ አያውቅም፤ ቨርን ድካም ቢሰማው ለረዥም ጊዜ ከአንድ ቦታ ሳይንቀሳቀስ በመቀመጡ ዘወትር አቀርቅሮ ሲፅፍ በመዋሉ እንጂ ከቦታ ቦታ በመዘዋወሩ አልነበረም። ቨርን ለ40 ዓመታት ያህል አሜንስ ከተማ ከነበረው መኖሪያ ቤቱ ህንፃ ውስጥ ካለችው አነስተኛ መፃፊያ ፎቅ ቤት ሳይወጣ ተቀምጧል። በእነዚህ አራት አስርት ዓመታት ውስጥ ቢያንስ በመንፈቅ አንድ መፅሀፍ ይፅፍ ነበር።

ዡሌስ ቨርን ታላቅ ነብይ ነበር። መጪውን ዘመን በብዕሩ መነፅር አቅርቦ፣ ተንትኖና ፈትሾ የሚያቀርብ የልብወለድ ደራሲ። ሬዲዮ ከመፈልሰፉ በፊት ቨርን የራሱ ቴሌቪዥን ነበረው። ስሙንም ፎኖቴሌፎቶ (phonotelephoto) ብሎ አወጣለት። ወንድማማቾቹ እነ ራይት የመጀመሪያይቱን አውሮፕላን ሰርተው ከማብረራቸው 50 ዓመት ቀደም ብሎ ቨርን ሂሊኮፕተሮች ነበሩት። ቨርን የኖረው በንግሥት ቪክቶሪያ ዘመን (በኛ በአፄ ቴዎድሮስ ዘመን አካባቢ) ቢሆንም ብዙዎቹን የሃያኛው ክፍለ ዘመን የሳይንስ ግኝቶች በቅድሚያ በብዕሩ ለመተንበይ የቻለ ደራሲ ነበር። ባህር ሰርጓጅ መርከቦች፣ አውሮፕላኖች፣ ባለህብረ ቀለም መብራቶች፣ (አምፑሎች) ማቀዝቀዣዎች፣ ሰማይ ጠቀስ ፎቆች፣ ዒላማ አስተካካይ ሚሳይሎች፣ ታንኮች፣ ወዘተ በብዕሩ የፈጠረ የሳይንስ ልብወለድ ድርሰት አባት ነበር።

የዡሌስ ቨርን ድርሰቶች እጅግ የመጠቁና አስደናቂዎች ከመሆናቸው የተነሳ በወቅቱ ምሁራንን አከራክረዋል፤ አሟግተዋልም። በርካታ የሂሳብና የፊዚክስ ጠቢባን የቨርንን ሳይንሳዊ ፅሁፎች በሂሳብ ስሌት ለማረጋገጥ ለሳምንታት መታገል ነበረባቸው። በድርሰቶቹ ይዘት የረኩ በርካታ ሊቃውንት ለቨርን የነበራቸውን ክብርና የላቀ አድናቆት ገልፀውለታል። አድሚራል ባይርድ በሰሜን ዋልታ ላይ በረራ አድርጎ እንደተመለሰ የጉዞው መሪና ኮምፓስ ዡሌስ ቨርን እንደነበር መስክሮለታል። የባህር አርክቴክት በመባል የሚታወቀው ሲሞን ሌክ በፃፈው የራሱ የህይወት ታሪክ የመጀመሪው አረፍተ ነገር ውስጥ «ዡሌስ ቨርን የህይወቴ መስመር ቀያሽ ነበር» የሚል ሀረግ ይገኝበታል።

ኦውገስት ፒካርድ የተባለው እውቅ የባህር አሳሽና ባሎኒስት፣ የሽቦ (ገመድ) አልባ ስልክ (ቴሌግራፍ) አባት ማርኮኒና ሌሎች የፈጠራ ሰዎች ለሰርዋቸው ስራዎች የሀሳባቸው ምንጭ መነሻ ቨርን መሆኑን በጋራ መስክረዋል። ዝነኛው ፈረንሳዊው ማርሻል ሊያዩ ተይ በአንድ ወቅት ለአገሩ ፓርላማ ባደረገው ዲስኩር «ዘመናዊ ሳይንስ ማለት ባጭሩ ቨርን በፅሁፍ ያሰፈረውን በገቢር ማሳየት ማለት ነው» ሲል ተናግሮ ነበር።

ዡሌስ ቨርን እድለኛም ነበር። ለወደፊት ይሆናሉ (ይሰራሉ) ብሎ በብዕሩ ትንቢት ካሰፈራቸው የቀለም ንድፎች ብዙዎቹ ወደ ተግባር ሲለወጡ በዓይኑ ለማየት ችሏል። ቨርን ራሱ «አንድ ሰው በሀሳቡ (በመላምት) ይሆናል ብሎ የሚገምተውን ሌላው ወደ ተግባር ይለውጠዋል» የሚል የዘወትር አባባል ነበረው።

ቨርን የተወለደው ናፖልዮን እንደሞተ እ.ኤ.አ በ1828 ናንቴ አጠገብ ነበር። ዊልንግተን የእንግሊዝ ጠቅላይ ሚኒስትር የነበሩበት ዘመን መሆኑ ነው። ያኔ የመጀመሪያው የባቡር መንገድ ከተሰራ ገና አምስት ዓመት ማስቆጠሩ ነበር። በወቅቱ መርከቦች በእንፋሎች ሞተር መጠቀም የጀመሩበት ጊዜ ቢሆንም አትላንቲክ ውቅያኖስን ለማቋረጥ ግን ሞተሮቻቸውን የሚያግዙ በነፋስ ኃይል የሚሰሩ መቅዘፍያዎች መጠቀም ነበረባቸው።

ዡሌስ በልጅነቱ ጊዜ ጎበዝ፣ ደፋር፣ አእምሮ ብሩህና ግድ የለሽ አይነት ሰው ነበር። አስራ ስምንት ዓመት ሲሞላው አባቱ የህግ ተማሪ እንዲሆን ወደ ፓሪስ ላኩት። የእርሱ ስሜትና ዝንባሌ ግን ወደ ግጥምና ቴአትር በማድላቱ የአባቱ ምኞት ሳይሳካ ቀረ። ከእለታት አንድ ቀን የጀሌስን ህይወት የቀየረ አጋጣሚ ተፈጠረ። በዚያች ቀን ዡሌስ በአንድ ህዝባዊ ውይይት ላይ ይሳተፍ ነበር። በመሀሉ ስብሰባው አልጥምህ ሲለው ጥሎ ወጣ። የነበረበትን የአዳራሽ ደረጃ ወርዶ ሲጨርስ መተላለፊያ ኮሪደር ላይ ከአንድ ግዙፍ ሰው ጋር ፊት ለፊት ተገናኙ። በዚያች አጋጣሚ ነበር ከደራሲ አሌክሳንደር ዱማስ ጋር የተዋወቀው። ዱማስ የቨርንን የመፃፍና የደራሲነት ፍላጎት ደገፈለት። አብረውም አንድ ቴአትር ፃፉ። ቴአትሩም በህዝብ ዘንድ ተወዳጅነት አገኘ። ከዚያ በኋላ ቶማስ በታሪክ ላይ ሲያተኩር ቨርን በጂኦግራፊ ላይ አነጣጠረ። በመጨረሻ ቨርን በአባቱ አጋዥነት በአስመጪነትና ላኪነት ሥራ ተሰማራ። በአጭር ጊዜ ውስጥም ብዙ ገንዘብ አገኘ።

እንደዚያም ሆኖ አብዛኛውን ጊዜውን የሚያሳልፈው ሁለት አነስተኛ ክፍሎች ባሏት ቤት ተቀምጦ ድርሰት በመፃፍ ነበር። ዘወትር ከማለዳው 12 ሰዓት ላይ ብእርና ወረቀት እንደያዘ ጠረጴዛው ላይ ነው። ያኔ ዡሌስ ለአንድ የህፃናት መፅሄት ሳይንሳዊ ፅሁፎችን ያዘጋጅ ነበር። አስር ሰዓት አካባቢ የዘመኑ መኳንንት የሚለብሱትን ልብስ ለብሶ ወደ

ቢሮው ይሄዳል::
የዡሌስ የመጀመሪያዋ መፅሀፍ «አምስት ሳምንታት በባቢሎን ውስጥ» የምትል ነበረች:: ለማሳተም ሲሞክር አሥራ አምስት አሳታሚ ድርጅቶች መፅሀፏ ብቃት የላትም ብለው መለሱበት:: በመጨረሻ ቨርን ተበሳጨና መፅሀፏን እሳት ላይ ወረወራት:: ድርጊቱን ስትከታተል የነበረችው ሚስቱ መፅሀፏን ፈጥና ከእሳት አነሳቻትና ባልዋን አፅናናችው:: ለመጨረሻ ጊዜ ሌላ አሳታሚ ዘንድ ሄዶ እንዲሞክርም ነገረችው:: በእርግጥም አሥራ ስድስተኛው አሳታሚ ተቀበለው::
አምስት ሳምንታት በባቢሎን ውስጥ ታትሞ በትወጣ በአንባብያን ዘንድ እጅግ ተወዳጅና ተወዳዳሪ የሌላት መፅሀፍ ሆና ተገኘች:: በዘመኑ እጅግ በርካታ በሆኑ ሌሎች ቋንቋዎች እየተተረጐመች መላውን ዓለም አዳረሰች:: በዚህች መፅሀፉ ሳቢያ ደራሲው 34 ዓመት ሲሞላው (በ1862) ዝነኛና ታዋቂ ሆነ:: የላኪና አስመጪነት ስራውንም ትቶ በዓመት ሁለት ልብ ወለድ መፅሀፍትን ለመፃፍ ኮንትራት ተፈራርሞ ሙሉ በሙሉ ወደ ድርሰት ዓለም ገባ:: ሁለተኛውን ቮየጅ ቱ ዘሰንተር ኦፍ ዘ ኤርዝ የሚለውን መፅሀፍ የፃፈው ከዚህ በኋላ ነበር:: በዚህ ድርሰቱ ቨርን የፈጠራቸው ገፀ ባህርያት አይስላንድ ከሚገኘው የእሳተ ጐመራ አፍ ገብተው እጅግ አስቸጋሪ በሆነው፣ በቀለጠና በጋለ ባህር ውስጥ ተጉዞ ጣልያን በሚገኘው ሌላ የእሳተ ጐመራ ተራራ አፍ እንዴት እንደወጡ ያሳያል:: ዡሌስ በዚህ ድርሰቱ የሰው ልጅ በሳይንስ እየታገዘ ሊሰራቸው የሚችላቸውን ተአምራት ቁልጭ አድርጐ ተነቦ በማይሰለች ቋንቋ ፅፏቸዋል::
በወቅቱ የሲውዝ ካናልን ሥራ አጠናቅቆ የነበረው ፌርዲናንድ ዴ ሌስፕስ በቨርን ድርሰት እጅግ ከመደነቁ የተነሳ ታላቁን የፈረንሳይ የክብር ኒሻን እንዲሸለም አስተዋፅኦ አድርጐለታል:: ቨርን የመጀመሪያ ልጁን እንደወለደ ከቤተሰቡ ጋር ከፓሪስ ወደ አሜንስ ተዛወረ:: እዚያም ገንዘብ እንደጐርፍ ይጐርፍለት ጀመር::
ዡሌስ በወቅቱ በትልቅነቷ ተወዳደሪ ያልነበራትን ጀልባ ገዛ:: ባለፎቅ መኖሪያ ህንፃም አሰራ:: በተለይ ፎቅ ላይ የመርከብ ካፕቴን ክፍል አይነት ቅርፅ ያላት ትንሽ ቤት ነበረችው:: ቨርን በዚያች ዙሪያዋ በተለያዩ ካርታዎችና መፃህፍት በተከበበው አነስተኛ ክፍል ውስጥ ነበር ቀሪዎቹን 40 ዓመታት ያሳለፈው::
ቨርን ከፃፋቸው በርካታ ድርሰቶቹ መካከል በአንባብያን ዘንድ ተደናቂነትን ያተረፈው «ሰማንያ ቀናት በዐለም ዙሪያ» የሚለው ነው:: በዚህ መፅሀፍ ቨርን በዋና ገፀ ባህርይ አስቀምጦት የነበረው ፊሊያስ ፎግ በወቅቱ በአንባብያን ሥነ ልቦና ፈጥሮት የነበረ ልዩ ስሜት ተወዳዳሪ አልነበረውም:: ሊታመን በማይችልና ልብ ሰቃይ በሆነ አገላለፁ የተሳቡ በርካታ አንባብያን ከኒውዮርክ፣ ከሎንደን በየቀኑ የፎግን ሁኔታ በቴሌግራም፣ በፖስታና በተለያየ መልክ አሳታሚውን ድርጅት በመጠየቅ ያስጨንቁት ነበር::
ይህ የሆነው በ1972 ነበር:: ከ17 ዓመት በኋላ አንድ የኒውዮርክ ጋዜጣ ኔሊ ብላይ የተባለች ሪፖርተሩን ዓለምን በአጭር ጊዜ በመዞር የፊለያስ ፎግን ሪኮርድ እንድትሰብር ላካት:: ብላይ ዓለምን በ72 ቀናት ለመዞር ቻለች:: በኋላም ሳይቤርያን አቋርጦ የሚያልፍ የምድር ባቡር ሀዲድ በመዘርጋቱ አንድ ፈረንሳዊ ዓለምን በ43 ቀናት ብቻ ለመዞር ችሏል:: በነገራችን ላይ ቨርን ሳይቤሪያን የሚያቋርጥ ባቡር መንገድ እንደሚሰራ የተነበየው ከመሰራቱ በርካታ ዓመታት ቀደም ብሎ ነበር::
«ሃያ ሺህ ሰዎች በባህር ስር» በሚለው መፅሀፉ ቨርን ባህር ሰርጓጅ መርከብን በህሳቡ ሰራ:: መርከብዋንም (ናዮቲላስ) ብሎ ጠራት:: የሚገርመው ባህር ሰርጓጅ መርከብ መፍጠሩ አልነበረም:: ዡሌስ በሀሳቡ የፈጠራት ናዮቲላስ በኋላ በሃያኛው ክፍለ ዘመን እንደተሰሩት እውነተኛ ባህር ሰርጓጅ መርከቦች ፎቅና ምድር ቤት ያላት፣ ራሷ ከባህሩ በምታመነጨው የኤሌክትሪክ ኃይል የምትንቀሳቀስና የዘመኑ የአሜሪካ ባህር ኃይል የሚጠቀምባቸው በአቶሚክ ኃይል እንደሚሰሩት እስከፈለገችው ጊዜ ድረስ ባህር ውስጥ ጠልቃ መቆየት የምትችል አይነት ነበረች::
ፈረንሳዊው «የቀለም ጀግና» የኋላ ኋላ በአሜሪካ ፍቅር እየተማረከ መጣ:: በአሜሪካ የኢንጂነር ኢንተርፕራይዞች፣ በአሜሪካ መልክአ ምድር ተሳበ:: ከዜጐችዋም ዋሽንግተንና ሊንከንን ከልብ ያደንቃቸው ነበር::
እንዲያውም ዡሌስ በህይወቱ ካፈራቸው ንብረቶቹ ሁሉ አስበልጦ የሚያከብራት ከኋይት ሀውስ የተላከችለትን ደብዳቤ ነበር:: ከዚያች በኮርሚት ሮዝቬልት (የፕሬዚዳንት ቴዶር ሮዝቬልት ልጅ) ፊርማ ከተላከችለት ደብዳቤ ውስጥ «አባቴ (ቴዎድር ሮዝቬልት) መፃህፎችህን በሙሉ እንዳነበባቸውና እጅግም እንደወደዳቸው እንድገልፅልህ ነግሮኛል» የሚል አረፍተ ነገር አለበት:: ዡሌስ ቨርን ከፃፋቸው በርካታ መፃህፍት መካከል እጅግ ተደናቂ የሆነችው ነገር ግን ደግሞ ብዙ ሰው ያላነበባት «የአሜሪካን ጋዜጠኛ የእለት ማስታወሻ በ2890» የምትለዋ ናት:: ዡሌስ በዚህች ድንቅ መፅሀፍ ኒውዮርክን ሁሉ አቀፍ (የጋራ) ከተማ ይላታል:: የዓለም ዋና ከተማ እንደምትሆንም ይተነብይላታል:: አውራ ጐዳናዎቿ 100 ያርድ ስፋት ሲኖራቸው ሰማይ ጠቀስ ህንፃዎቿ 1000 ጫማ ያህል ቁመት ይረዝማሉ::
በዚህን ጊዜ የዓለም የአየር ንብረት በተፈጥሮ መሆኑ ቀርቶ በሰው ቁጥጥር ሥር ይሆናል:: አዝርእት በሰሜናዊ ዋልታ ጫፍ ይበቅላሉ (እህል ይመረታል) ጋዜጠኞች ከደመና ላይ ሆነው ዜናና ማስታወቂያዎችን ያቀነባብራሉ:: የዡሌስ ጀግና (ገፀ ባህርይ) 80 ሚልዮን አንባብያን ያሉትን «የምድር ሄራልድ» የተባለውን ጋዜጣ ኤዲት ያደርጋል:: የሄራልድ ሪፖርተሮች ከጁፒተር፣ ከማርስና ከቬኑስ ፕላኔቶች ሆነው ዜና በቴሌቪዥን ያስተላልፋሉ:: ጋዜጠኞቹ ይህን ሁሉ ሲያደርጉ የመሬት ተመልካቾች ድርጊታቸውን በቀጥታ ይከታተላሉ::
ዛሬ ይህንን የቨርን ፅሁፍ የሚያነብ ሰው ድርሰቱ ከዛሬ 100ና 130 ዓመት በፊት የተፃፈ ነው ብሎ ለማመን ይከብደዋል:: ዡሌስ ቨርን በመጨረሻው የህይወት ዘመን ደስተኛ አልነበረም:: ምሁራን በምቀኝነት መንፈስ ከበቡት:: በዚህ የተነሳ በወቅቱ በፈረንሳይ ምድር ዡሌስ ቨርንን የሚወዳደር ተወዳጅ ደራሲ ያልነበረ ቢሆንም ለፈረንሳይ አካዴሚ ሳይመረጥ ቀረ:: ከዚያ በኋላ ቨርን በስኳር በሽታ ተለከፈ:: ዓይኖቹ አልሰራ አሉ:: ጆሮውም ከዳው:: የመጨረሻዎቹ ፅሁፎቹ ጭሰኞችና ላብአደሮች ስልጣን ላይ እንደሚወጡ በሚያሳዩ አገላለፆች የተሞሉ ነበሩ::
በመጨረሻ ዡሌስ ቨርን መጋቢት 24/1905 (እ.ኤ.አ) አረፈ:: የዓለም ህዝብ አለቀሰለት:: በቀብሩ ስነስርዓት ላይ የበርካታ አገሮች ዲፕሎማቶች፣ የነገሥታትና የፕሬዚዳንቶች ተወካይ ልኡካን፣ በህይወቱ እያለ በነገር ሲጐጭቁት የነበሩት 40ዎቹ የፈረንሳይ አካዴሚ አባሎች፣ በብዙ ሺህ የሚቆጠሩ የብዕሩ አድናቂዎች ተገኝተዋል::
ዡሌስ ከመሞቱ ትንሽ ቀደም ብሎ «ዘለዓለማዊው አዳም» የሚለውን ድንቅ መፅሀፉን ፅፎ ጨርሶ ነበር:: ዡሌስ ቨርን በብዕሩ የተነበያቸው አብዛኞዎቹ በተግባር ውለዋል:: ማን ያውቃል? በ2890 ዓ.ም ደግሞ ስንዴና በቆሎ በሰሜናዊ ዋልታ የበረዶ ማሳዎች ይበቅሉ ይሆናል:: ማን ያውቃል? የሰው ልጅ በደመና ላይ ሊራመድ፣ እዚህ ውሎ ማርስ ላይ ሊያድር ይችል ይሆናል::






# ጥሩ ሐሳብ

## ጥሩ ዕቃ በጥሩ ዋጋ/የመኪና ጭስ ማውጫና ማፈኛ

## ከዚህ በፊት በኢትዮጵያ ያልነበረ አገልግሎት መስጠት ጀምረናል::

እንኳን ደስ ያላችሁ!

የጭስ ማውጫና የድምፅ ማፈኛ ችግራችሁን ሁሉ የሚያስወግድ ድርጅት ተከፈተላችሁ!!

በሀገራችን ውስጥ ያሉት አብዛኛዎቹ ተሽከርካሪዎች ከሚያጋጠማቸው ችግሮች አንዱ **ጭስ ማውጫና የድምፅ ማፈኛ** በየጊዜው መቀደድና መበላሸት ነው::

ይህንን በመገንዘብ ቴልኮ የግል ማህበር በዩናይትድ ስቴትስ ኦፍ አሜሪካ ውስጥ ጥሩ ስም ካፈራው **IPC-Huth** ከሚባለው **ለ-MIDAS** አቅራቢ ኩባንያ ጋር በመተባበር ለተለያዩ ተሽከርካሪዎች የሚሆኑ **የድምፅና የጭስ ማፈኛ ሲስተም አቅርበናል::**

**የድምፅ ማፈኛ** ሁለት መሠረታዊ አገልግሎቶች አሉት:: እነርሱም፤

1. የሞተር ድምፅን በመቀነስ መኪናዎች በጸጥታ እንዲሽከረከሩ ይረዳል::
2. ከሞተሩ ሲወጣ በማፈን ለሞተሩ ተጨማሪ ግፊት በመስጠት ተሽከርካሪዎች የበለጠ ጉልበት እንዲያገኙ በትክክል እንዲሰሩና ነዳጅ እንዲቆጥቡ ያደርጋል::

አዲስ የጭስ ማውጫና የድምፅ ማፈኛ ሲገዙ የሁለት ዓመት ዋስትና እንደምንሰጥዎ አይዘንጉ::

መኪናዎ በአማካኝ 16,000 ኪሎ ሜትር በዓመት ይሽከረከራል እንበልና በሊትር 8 ኪሎ ሜትር ቢሄድ በዓመት 2,000 ሊትር ነዳጅ ያስፈልግዎታል:: በጊዜው የነዳጅ ዋጋ (በሊትር ብር 2.51) በዓመት 5,020 ብር ለነዳጅ ያወጣሉ ማለት ነው:: ነገር ግን ከድምፅና ጭስ ማፈኛው ጥራት ማነስ የተነሳ ለሞተሩ በቂ ግፊት ባለመስጠቱ መኪናዎ በሊትር 7 ኪሎ ሜትር ከሄደ በዓመት የሚያስፈልግዎ 2,286 ሊትር በመሆኑ ለነዳጅ 5,737.86 ብር ያወጣሉ:: በዚህ የተነሳ 718 ብር በዓመት ይከስራሉ ማለት ነው:: ስለዚህ የመኪናዎን ድምፅ ማፈኛ በዓመት ከሚከስሩት ባነሰ ገንዘብ በመቀየር የነዳጅ ወጪዎን ይቀንሱ::




የተሻለ ግንዛቤ ለማግኘት አምቼ አካባቢ ወደሚገኘው ድርጅታችን ብቅ ይበሉ::



☎ 61 51 90 /1/2
ፋክስ 61 51 23
ፖ.ሣ.ቁ. 2287
አዲስ አበባ፣ ኢትዮጵያ

## ቴልኮ ኃ.የተ.የግ.ማ.

---

# ወንዶ የንግድ ኩባንያ

ወንዶ የንግድ ኩባንያ እስከ አርሶአደሩ መንደር ድረስ ዘልቆ በመግባት በታጠበና በደረቅ ቡና ንግድ፣ በማዳበሪያ አቅርቦት፣ ምርጥ ዘርና የእህል ምርቶችን ለገበያ በማቅረብ ሥራ ተሰማርቷል:: የአዲስ ጎማ ምርቶችንም በውክልና ያከፋፍላል:: የእርሻ ምርቶችና የኢንዱስትሪ ውጤቶችን ለላኪዎች፣ እንዲሁም ሌሎች ለፋብሪካዎች፣ ለጅምላ አከፋፋዮች፣ ለቸርቻሪዎችና ለተጠቃሚዎች ያቀርባል:: በተጨማሪም በዘመናዊ የንግድ ሥራ ጥበብ በተካኑ ባለሙያዎች በቅልጥፍና ሊያገለግልዎ ምንጊዜም ዝግጁ ነው::
ሥራዎን ወደ ደቡብ ኢትዮጵያ በተለይም ወደ ገጠሩ ሕብረተሰብ ማስፋፋት ሲፈልጉ አስተማማኝ አቅራቢዎና ወኪልዎ ወንዶ የንግድ ኩባንያ መሆኑን አይዘንጉ::

**አድራሻ** ዋናው መ/ቤት ስልክ (06) 201426 , (06)201623 , (06)201062 , 06)201590
ፋክስ (06) 201949 ፖ.ሳ.ቁ 128 አዋሳ
አ/አ ቅርንጫፍ ስልክ (01) 150248 ፋክስ (01) 513654, ፖ.ሣ.ቁ. 9515 አ/አ
ዲላ ቅርንጫፍ ስልክ (06) 311031 ዲላ
ሰሜን ኦሞ ቅርንጫፍ ስልክ (06) 510479 ወላይታ ሶዶ
ሆሳእና ቅርንጫፍ ስልክ (06) 550342

ወንዶ የንግድ ኩባንያ

# የጣና ሐይቅ ትራንስፖርት ድርጅት



ድርጅታችን:-

1. በጣና ሐይቅ ሰውንና እቃን በተመጣጣኝ ዋጋ ከቦታ ወደ ቦታ እናጓጉዛለን:
2. ምቹና ዘመናዊ በሆኑ ጀልባዎቻችን ደሴቶችንና ታሪካዊ ቦታዎችን እናስጎበኛለን
3. በእንግዶቻችን «ምድረገነት» በሚባልለት ሆቴላችን ቢንጉና ማንጉ መናፊሻዎቻችን
   ለስፖርት ማዘውተፊያዎች
   ለስብሰባ ለግብዣ ለሠርግ
   የተሟላ ዝግጅት ያለውና ከውጭ በመጡ እንግዶች ዘንድ አድናቆትን ያተረፈ ነው::





4. በጉረጉራ ወደብ ወርክ ሾፕ
   ማንኛውንም የሞተር ጥገና እናደርጋለን
   የቤትና የቢሮ እቃዎችን በትእዛዝ
   እንሰራለን በተመጣጣኝ ዋጋና በረዥም ጊዜ ክፍያ እናስተናግዳለን::

**ለማንኛውም የኤሌክትሪክ ሞተሮች የሪዋይንዲንግ አገልግሎት እንሰጣለን::**




አድራሻችን
ስልክ ባሕርዳር
08 - 20 00 06 / 08 - 20 00 27
08 - 20 07 30
ጉረጉራ 7፤ 2
ፖ.ሣ.ቁጥር 9



# የጣና ሐይቅ ትራንስፖርት ድርጅት






## ዩኒ-ማግ ኃ.የተ.የግ.ማ.
## UNI-MAG PVT. LTD. CO.

Tel. 653537, 653538
Fax 251-1-654965
P. O. Box 25780
Addis Ababa, Ethiopia

አድራሻ :-
ወሎ ሠፈር ፀሀይ አጠገብ

ለማንኛውም ዓይነት የእንጨት ሥራ
ዘመናዊ የእንጨት ሥራ ማሽኖች

**WE SUPPLY THESE AND MANY MORE !**



የተለያዩ መጠን ያላቸው ጄነሬተሮች





የተለያዩ የኮንስትራክሽን ማሽኖች

ፓወር ቱልስ







**ITALIA line**

ማሽነሪዎች ማቅረብ ብቻ ሳይሆን:-
* ምን አይነት ማሽን እንደሚያስፈልግዎ የምክር አገልግሎት መስጠት
* የተሟላ የጥገና አገልግሎት
* የዋስትና ጊዜም እንሰጣለን



ብርሃንና ሰላም ማተሚያ ድርጅት ታተመ